# ማውጫ

ማውጫ ገፅ

## የጥሞናን ጊዜን የምትለማመድበት መንገድ

**1. የንባብ ክፍል ዮሐንስ 1፤1−8 ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፡− ቃል ሥጋ ሆነ**

1. በመጀመሪያ ቃል ነበረ፣ ቃልም ከእግዚአብሔር ጋር ነበረ፣ ቃልም እግዚአብሔር ነበረ።

2. ኢየሱስም በመጀመሪያ ከእግዚአብሔር ጋር ነበረ።

3. ሁሉ ነገር በኢየሱስ ተፈጥሮአል፣ ከተፈጠረው ሁሉ፣ አንድም ነገር ያለ ኢየሱስ የተፈጠረ የለም።

4. በኢየሱስ ሕይወት ነበረ፣ ይህም ሕይወት የሰዎች ብርሃን ነበረ።

5. ብርሃንም በጨለማ ይበራል፣ ጨለማም አላሸነፈውም።

6. ከእግዚአብሔር የተላከ ስሙ ዮሐንስ የሚባል አንድ ሰው ነበረ፤

7. ዮሐንስ ይህ ስለ ብርሃን ይመሰክር ዘንድ በእርሱ በኩል ሰዎች ሁሉ ለምስክር መጣ።

8. ዮሐንስ ስለ ብርሃን ሊመሰክር መጣ እንጂ፣ ዮሐንስ ብርሃን አልነበረም።

**ቁ**.1−2 ቃል በመጀመሪያ ከእግዚአብሔር ጋር ነበር። በመጀመሪያ ቃል(ኢየሱስ) ከእግዚአብሔር ጋር አቻ ሥራዎችን ሠራ። ኢየሱስ ወደ ዓለም የመጣው እግዚአብሔር ማን እንደ ሆነ ለእኛ ለመግለጽ ነበር። ስለዚህ እኛ በቃሉ ውስጥ እግዚአብሔርን ለማወቅ የሕይወት ዕውቀትን እንቀበላለን።

**ቁ**. 3 ቃል (ኢየሱስ) ከእግዚአብሔር ጋር ዓለምን ፈጥሯል። ስለዚህ ኢየሱስ ፈጣሪ ነው እንጂ ፍጡር አይደለም። ኢየሱስ ዓልፋና ኦሜጋ፣ መጀመሪያና መጨረሻ ነው። (ራዕ.22፥13) ኢየሱስ ከዓለም መጀመሪያ ጀምሮ እስከ አዲስ ፍጥረት ሁሉ የተሠሩት ሥራዎችን የሚያስተዳድር ነው። ዛሬ የኢየሱስ ሥራ ሰዎችን ከኃጢአት ማዳን ነው። የእኛንም ሕይወት ኢየሱሱ አዲስ አድርጎ እንዲፈጥር እንናፍቃለን። ማንም ሰው ኢየሱስን ካመነ ያ ሰው አዲስ ፍጥረት ነው። (2ቆሮ. 5፥17) ለእኛ እምነትን የሰጠውን እንዲሁም አዲስ ፍጥረት ያደረገውን ኢየሱስን እናመሰግናለን።

**ቁ**. 4-5 **ኢየሱስ ሕይወትና ብርሃንን ይዞ መጣ። ኢየሱስ ከጨለማ ሰዎችን ለማዳንና የሕይወትን ብርሃን ለመስጠት መጣ። ይህ ብርሃን(ኢየሱስ) ሕይወታችንን በብሩህ እንዲያበራና እግዚአብሔርን እንድናውቅ ዕውቀት እንዲሞላልን እንጸልያለን።**
**ቁ**. 6-8 **ይህ ብርሃን ዮሐንስ አይደለም። ነገር ግን እርሱ ስለ ብርሃን የሚመሰክር ሰው ነው። ዛሬ እኛ በየትኛውም ቦታ ስንሠራ የኢየሱስን ቦታ አንሰርቅም። ነገር ግን ኢየሱስን ብቻ እንድንገልጽ ቃል ኪዳን እናደርጋለን።**
**እንጸልይ፡- ጌታ ሆይ! ዛሬ እኛ የኢየሱስ ብርሃንን ሳንክድ ነገር ግን በብርሃን መካከል እየሄድን ስለ ኢየሱስ የምንመሰክር ሰዎች አድርገን።**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

2. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 1፥9−18 **ወር፦ ቀን፦**

**ርዕስ፦− የመጀመሪያ የመጥምቁ ዮሐንስ ምስክርነት**

9. **ለሰው ሁሉ የሚያበራው እውነተኛው ብርሃን ወደ ዓለም እየመጣ ነበር።**

10. **ኢየሱስም በዓለም ውስጥ ነበረ፣ ዓለምም የተፈጠረው በእርሱ ነው፣ ነገር ግን ዓለም አላወቀውም።**

11. **ኢየሱስ ወደ ራሱ ወገኖች መጣ፣ ነገር ግን የገዛ ወገኖቹ አልተቀበሉትም፣**

12. **ነገር ግን ኢየሱስ ራሱ ለተቀበሉትና በስሙ ላመኑት ሁሉ ሰዎች የእግዚአብሔር ልጆች የመሆን መብት ሰጣቸው።**

13. **እነርሱም ከእግዚአብሔር ተወለዱ እንጂ ከደም ወይም ከሥጋ ፈቃድ ወይም ከሰው ፈቃድ አልተወለዱም።**

14. **ቃልም ሥጋ ሆነ፣ በመካከላችንም ኖረ፣ እኛም ጸጋንና እውነትን ተሞልቶ ከአባቱ ዘንድ የመጣውን የአንድያ ልጅን ክብር አየን።**

15. **ዮሐንስ ስለ እርሱ መሰከረ እንዲህም ብሎ ጮኸ። "ከእኔ በኋላ የሚመጣው ከእኔ በፊት ስለ ነበረ ከእኔ እጅግ ይበልጣል ብዬ የነገርኳችሁ እነሆ፣ እርሱ ነው"**

16. **ከእርሱ የጸጋ ሙላት እኛ ሁላችን በጸጋ ላይ ጸጋን ተቀብለናል።**

17. **ሕግ በሙሴ በኩል ተሰጥቶ ነበር፣ ነገር ግን ጸጋና እውነት በኢየሱስ ክርስቶስ በኩል መጣ።**

18. **እግዚብሔርን ያየው ከቶ ማንም የለም፣ ነገር ግን በአብ እቅፍ ያለው አንድያ ልጁ የሆነው እርሱ ገለጠው።**

**ቁ**.10−11 **ኢየሱስ እውነተኛ ብርሃን ሆኖ ወደ ዓለም መጣ። ነገር ግን ሰዎች ናቁት። ኢየሱስ ዓለምን ሁሉ ፈጥሯል። ነገር ግን ዓለም ኢየሱስን አላወቀውም። ይህ የዓለም ታላቅ አሳዛኝ ሁናቴ ነው።**

− **ዛሬ ኢየሱስ ወደ እኛ ቢመጣ ለእግዚአብሔር እንዴት እንመልሳለን**?

**ቁ**. 14 **ኢየሱስ ሥጋ ሆኖ እንደ እውነተኛ ቤተ መቅደስ በእኛ ውስጥ አድሮ እግዚአብሔርን ገለጸ። ይህ እግዚአብሔርን የገለጸው ከጌታ ጋር ያለውን ግንኙነትና የቅርብ ወዳጅነትን ያስገነዝባል። ዛሬ የእግዚአብሔር ቤተ መቅደስ በእግዚአብሔር ክብር ተሞልቶ እንድናይ እንጸልያለን።**

**ቁ**. 14-18 ኢየሱስ ወደ ዓለም የሰውን ሥጋ ለብሶ በመምጣት እግዚአብሔርን ገለጸ። ይህ እኛ ያላየነውን እግዚአብሔርን የገለጸው ከራሱ ወገኖቹ ጋር ጥልቅ ኅብረት ስላደረገ ነበር። ዛሬ በእግዚአብሔር ፀጋና እውነት ከጌታ ጋር የቅርብ ወዳጅነት አለን።
**ቁ**. 15-18 ኢየሱስ ከፍጥረት ሁሉ በፊት ነበረ። የሙሴንም ሕግ እውነት መሆኑን እያስተማረ መጣ። ኢየሱስ የእግዚአብሔር ፀጋና የደንነት ስጦታ ሰጠ። ሙሴና መጥምቁ ዮሐንስ የእግዚአብሔር አገልጋዮች ነበሩ። ነገር ግን ኢየሱስ የእግዚአብሔር ልጅ በመሆኑ እግዚአብሔርን ፈጽሞ ገለጸ። ስለዚህ በየቀኑ እኛ በኢየሱስ ውስጥ እግዚአብሔርን ስላወቅን እግዚአብሔርን እየባረክን እንደሰታለን።
**እንጸልይ፦** ጌታ ሆይ! እኛ የእግዚአብሔርን ብዙ ፀጋና እውነትን ማየት እንድንችል እርዳን።

1. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ

2. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት

3. እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?

4. የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና

5. ትምህርት

6. ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)

7. ፀሎት

3. **የንባብ ክፍል    ዮሐንስ 1፥19−34 ወር፡         ቀን፡**

**ርዕስ፡−  ሁለተኛ የመጥምቁ ዮሐንስ ምስክርነት**

19. የአይሁድ ባለሥልጣኖች ከኢየሩሳሌም ካህናትንና ሌዋውያንን ወደ ዮሐንስ ልከው፣ “አንተ ማን ነህ?” ብለው ባስጠየቁት ጊዜ፣ የዮሐንስ ምስክርነት ይህ ነው።

20. ዮሐንስ መሰከረ አላለም፣ “እኔ ክርስቶስ አይደለሁም” ብሎ መሰከረ።

21. እነርሱም፣ “ታዲያ አንተ ማን ነህ? ኤልያስ ነህ?” ብለው ጠየቁት። ዮሐንስም፣ “አይደለሁም” አለ። እነርሱም፣ “ታዲያ ይመጣል የተባለው ነቢዩ ነህ?” አሉት። ዮሐንስም፣ “አይደለሁም!” አለ።

22. እነርሱም ለዮሐንስ እንዲህ አሉት፣ “ታዲያ አንተ ማን ነህ? ለላኩን ሰዎች መልሱን እንድንነግር ስለ ራስህ ምን ትላለህ?”

23. ዮሐንስም በነቢዩ በኢሳይያስ እንደተነገረው፣ እኔ፣ ‘የጌታን መንገድ አቅኑ!’ እያለ በምድረ በዳ የሚጮኽ ሰው ድምፅ ነኝ” መለሰ።

24. እነርሱ የተላኩት ከፈሪሳውያን ነበሩ፣

25. እነርሱ ለዮሐንስ ብለው እንዲህ ጠየቁት። “አንተ ክርስቶስ ወይም ኤልያስ ወይም ነቢዩ ካልሆንህ፣ ለምን ታጠምቃለህ?”

26. ዮሐንስም እንዲህ ብሎ መለሰላቸው፣ “እኔ በውሃ አጠምቃለሁ፣ ነገር ግን እናንተ የማታውቁት አንድ ሰው በመካከላችሁ ቆሞአል።

27. እርሱ ከእኔ በኋላ የሚመጣ ነው፣ እኔ የጫማውን ጠፍር ልፈታ የማይገባኝ፣ አላቸው።

28. ይህ ሁሉ ዮሐንስ ያጠምቅ በነበረበት ከዮርዳኖስ ወንዝ ማዶ በቢታንያ ነበር።

29. በማግስቱ ዮሐንስ ኢየሱስን ወደ እርሱ ሲመጣ አይቶ እንዲህ አለ፣ “እነሆ፣ የዓለምን ኃጢአት የሚያስወግድ የእግዚአብሔር በግ ይህ ነው!

30. ‘ከእኔ በኋላ የሚመጣው ከእኔ በፊት ስለ ነበር ከእኔ ይልቃል” ያልሁት እርሱ ነው፣

31. እኔም ራሴ አላውቀውም ነበር፣ ነገር ግን እኔ በውሃ እያጠመቅሁ የመጣሁትም እርሱ በእስራኤል ዘንድ እንዲገለጥ ነው።

32. ዮሐንስም እንዲህ ብሎ መሰከረ። “እኔ መንፈስ ቅዱስ እንደ ርግብ ከሰማይ ወርዶ በእርሱ ላይ ሲያርፍ አየሁ፣

33. እኔ ራሴ እርሱን አላውቀውም ነበር፣ ነገር ግን በውሃ እንዳጠምቅ የላከኝ እግዚአብሔር እንዲህ አለኝ፣ 'መንፈስ ቅዱስ ሲወርድና በእርሱ ላይ ሲያርፍበት የምታየው በመንፈስ ቅዱስ የሚያጠምቅ እርሱ ነው'
34. እኔም ይህን አይቻለሁ፣ ስለዚህ እርሱ የእግዚአብሔርን ልጅ መሆኑን እመሰክራለሁ።

ቁ. 29 ኢየሱስ የዓለምን ኃጢአት የሚሸከም ጠቦት ነው። እስራኤላዊያን ከግብጽ ሲወጡ ጠቦት በማረድ በእርሱ ደም የቤቱን መቃን በመቀባት ከሞት ዳኑ። በአዲስ ኪዳን ዘመን ኢየሱስ ራሱ የፋስካ ጠቦት በመሆን በመስቀል ላይ ሞተ። የእኛንም ኃጢአት አነጻ። ኢየሱስ በመስቀል ላይ ተሰቅሎ ደሙን በማፍሰስ ኃጢአታችንን ሁሉ ስላነጻ እናመሰግናለን።

ቁ. 30-34 ኢየሱስ በመንፈስ ቅዱስ እኛን አጠመቀን። ዮሐንስ በውሃ በሚያጠምቅበት ጊዜ ሰዎች ንስሓ ገብተው ኢየሱስን ተቀበሉ። ነገር ግን ኢየሱስ እኛን በመንፈስ ቅዱስ እንደገና ስለ ወለደን ኢየሱስ ክርስቶስን በልባችን በማመን ከእግዚአብሔር የዘላለም ሕይወትን ተቀበልን።

- የእግዚአብሔር ሕይወት በእኛ ውስጥ እንዴት ያድጋል?

ቁ. 19-23 አይሁዶች መጥምቁ ዮሐንስን "አንተ ማን ነህ" ብለው ስጠይቁት እርሱ እኔ ክርስቶስ፣ ኤልያስ፣ ነቢያትም አይደለሁም" በማለት መለሰ። ዮሐንስም እኔ የሰዎችን ልብ ወደ ክርስቶስ ሀሳብ ለመለወጥና የመሢሕን መንገድ ለማዘጋጀት የሚመሰክር ሰው ነኝ በማለት ደግሞ መለሰ። እኛ ስንሠራ ከሰዎች ምሥጋናን ውዳሴንና ክብርን ለማግኘት ነው? ወይስ ከእግዚአብሔር እነዚህን ለማግኘት ነው?

ቁ. 23 መጥምቁ ዮሐንስ በምድረ በዳ የእግዚአብሔርን መንገድ ለማዘጋጀት ይሰብካል። (ኢሳ. 40፡3) ኢየሱስ ቃል ነው፤ ነገር ግን ዮሐንስ የቃል ድምፅ ነው። በእኛ ሕይወት የእኛ ድምፅ ከጌታ ቃል ትልቅ ነው? የእኛ ድምፆቻችን ከእግዚአብሔር ቃል ይልቅ ትልቅ መሆን የለበትም።

**እንጸልይ፦ ጌታ ሆይ፤ የእግዚአብሔር በግ የሆነው ኢየሱስ የእኛን ኃጢአት ስላነጻ እግዚአብሔርን እናመሰግናለን፤ አሜን።**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

4. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ 1፥35-51 ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፡- የሚበልጠውን ሥራ ማየት**

35. በማግስቱ፣ ደግሞ ዮሐንስ ከሁለት ደቀ መዛሙርቱ ጋር እዚያ ቆሞ ነበር፣
36. ዮሐንስ ኢየሱስን በዚያ ሲያልፍ አይቶ እንዲህ አለ፣ "እነሆ፣ የእግዚብሔር በግ!"
37. ሁለቱ ደቀ መዛሙርትም ይህን ሲናገር ሰምተው ኢየሱስን ተከተሉት።
38. ኢየሱስም ዘወር ብሎ ሲከተሉት አየና፣ "ምን ትፈልጋላችሁ?" ብሎ ጠየቃቸው። እነርሱም፣ "ረቢ፣ የት ትኖራለህ?" አሉት፣
39. ኢየሱስም፣ "ኑና እዩ!" አላቸው። ስለዚህ ሁለቱ ደቀ መዛሙርትም ሄዱና የት እንደሚኖር አዩ። በዚያን ቀን ከኢየሱስ ጋር አብረው ዋሉ፣ ጊዜው ወደ አሥር ሰዓት ያህል ነበር።
40. ዮሐንስ የተናገረውን ቃል ሰምተው ኢየሱስ ከተከተሉት ደቀ መዛሙርት አንዱ የስምዖን ጴጥሮስ ወንድም እንድርያስ ነበር።
41. እንድርያስ በመጀመሪያ ያደረገው ወንድሙን ስምዖንን ፈልጎ፣ "እኛ ክርስቶስን አገኘነው!" አለው። ('መሲሕ' ማለት ክርስቶስ ማለት ነው።)
42. ከዚህ በኋላ እንድርያስ ስምዖንን ወደ ኢየሱስ አመጣው። ኢየሱስም ስምዖንን አይቶ እንዲህ አለው፤ "አንተ የዮና ልጅ ስምዖን ነህ፥ነገር ግን ከእንግዲህ ወዲህ ኬፋ ትባላለህ" ('ኬፋ' ማለት ጴጥሮስ ማለት ነው)
43. በማግስቱ፥ኢየሱስ ወደ ገሊላ ለመሄድ ፈለገ፣ ፊልጶስንም አገኘውና፣ "ተከተለኝ!" አለው፣
44. ፊልጶስም እንደ እንድርያስና እንደ ጴጥሮስ ሁሉ የቤተ ሳይዳ ከተማ ሰው ነበረ።
45. ፊልጶስ ናትናኤልን አግኝቶ እንዲህ አለው። "ሙሴ በሕግ መጽሐፍ፣ ነቢያትም በትንቢት መጻሕፍት ስለ እርሱ የጻፉለትን አገኘነው፣ እርሱም የዮሴፍ ልጅ የናዝሬቱ ኢየሱስ ነው"
46. ናትናኤልም፣ "ከናዝሬት በጎ ነገር ሊወጣ ይችላልን?" አለው። ፊልጶስም፣ "መጥተህ እይ!" አለው።
47. ኢየሱስም፣ ናትናኤል ወደ እርሱ ሲመጣ አይቶ፣ "እነሆ፣ ተንኰል የሌለበት እውነተኛ እስራኤላዊ ሰው!" ሲል ስለ እርሱ ተናገረ።
48. ናትናኤልም፣ "እንዴት ታውቀኛለህ?" ሲል ጠየቀው። ኢየሱስም፣ "ፊልጶስ ሳይጠራህ በፊት ከበለስ ዛፍ ሥር ሆነህ አየሁህ" ሲል መለሰለት።

49. በዚህ ጊዜ ናትናኤል መልሶ፣ “መምህር ሆይ! አንተ የእግዚአብሔር ልጅ ነህ! አንተ የእስራኤል ንጉሥ ነህ!” አለው።
50. ኢየሱስም እንዲህ መልሶ፣ “አንተ ያመንኸው፣ ከበለስ ዛፍ ሥር ሆነህ አየሁህ ስላልሁህ ነውን? ገና ከዚህ የሚበልጥ ነገር ታያለህ”
51. ኢየሱስ ጨምሮን እንዲህ አለው። “በእውነት እላችኋለሁ፣ ሰማይ ተከፍቶ፣ የእግዚብሔርም መላእክተ በሰው ልጅ ላይ ሲወጡና ሲወርዱ ታያላችሁ”

ቁ. 39 ኢየሱስ ደቀ መዛሙርቱን “ኑና እዩ” ብሎ ጠርቶ እንዲያውቁት ምቹ ጊዜ ሰጣቸው። ስለዚህ እነርሱ ሄደው በዚያን ቀን ከኢየሱስ ጋር አብረውት ዋሉ። ዛሬ ኢየሱስ ከእኛ ጋር ለመኖር ይጠራል። እኛ ኢየሱስ ሲጠራን የምንመልሰው መልስ ምንድን ነው?

ቁ. 41−42 ኢየሱስ የሰዎችን ሕይወት ይለውጣል። ለጴጥሮስ ዓለት እንዲሆን ተስፋ ሰጠው። የእኛንም ሕይወት እንዲለውጥ እግዚአብሔርን እንናፍቃለን።

ቁ. 47−48 ኢየሱስ እራሱ የናትናኤልን ልብ አይቶ “እነሆ፣ ተንኰል የሌለበት እውነተኛ የእስራኤል ሰው!” በማለት ተናገረ ኢየሱስ የሰዎችን ልብ ሁሉ ያውቃል። ዛሬም የልባችንን ሀሳብ ተመልክቶ ምን ይላል?

ቁ. 49 ኢየሱስ የእግዚአብሔር ልጅና የእስራኤል ንጉሥ ነው። የናትናኤል ኑዛዜ ከዮሐንስ ምስክርነት ጋር አንድ ዓይነት ነው። (ዮሐ. 1፡34) እኛ እንደዚሁ መናዘዝ አለብን። (20፡31) እኛ ለእግዚአብሔር የተናዘዝነው ነገር ምንድን ነው?

ቁ.50−51 ኢየሱስ ለናትናኤል ታላቅ ሥራ እንዲያይ ተስፋ ሰጠው። ይህ ኢየሱስ በእግዚአብሔርና በሰዎች መካከል እንደ መሰላል ነው። ስለዚህ እኛ መንገድ እውነት ሕይወት በሆነው በኢየሱስ በኩል ከእግዚአብሔር ክብርንና ሙሉ ግንኙነትን እንቀበላለን።

**እንጸልይ፡– ጌታ ሆይ! የእምነት ዓይኖቻችን ተከፍቶ እግዚአብሔር ገልጾ የሰጠውን ታላቅ ሥራን መመልከት እንድንችል እርዳን።**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

5. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 2፥1−11 **ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፡− የኢየሱስ ክርስቶስ የመጀመሪያ ተአምራት**

1. **በሦስተኛው ቀን፣ በገሊላ አውራጃ፣ በቃና ከተማ ሠርግ ነበረ፣ የኢየሱስም እናት በዚያ ነበረች፣**

2. **ኢየሱስና ደቀ መዛሙርቱም ወደ ሠርጉ ተጠርተው ነበር።**

3. **በሠርጉ ግብዣ ላይ የወይን ጠጅ ባለቀ ጊዜ የኢየሱስ እናት ኢየሱስን፣ "የወይን ጠጅ አልቆባቸዋል እኮ!" አለችው።**

4. **ኢየሱስም እንዲህ አላት። "እናቴ ሆይ! ከአንቺ ጋር ምን አለኝ? ጊዜዬ ገና አልደረሰም"**

5. **በዚያን ጊዜ እናቱ እዚያ ለነበሩት አገልጋዮች "እርሱ የሚላችሁን ሁሉ አድርጉ!" አለቻቸው።**

6. **አይሁድ የመንጻት ሥርዓት ስለ ነበራቸው ስድስት የድንጋይ ጋኖች በዚያ ነበሩ፣ እያንዳንዱ ጋን ሁለት ወይም ሦስት እንስራ ውሃ ለመያዝ ይችል ነበር።**

7. **ኢየሱስ አገልጋዮቹን እንዲህ አላቸው፣ "ጋኖቹን ውሃ ሙሉአቸው!" እነርሱም እስከ አፋቸው ሞሉአቸው።**

8. **ከዚህ በኋላ ኢየሱስ አገልጋዮቹን አላቸው፣ "አሁን ውሃን ቀድታችሁ ለአሳዳሪው ስጡት!" እነርሱም ወስደው ሰጡት።**

9. **የድግሱ ኀላፊም ወደ ወይን ጠጅ የተለወጠውን ውሃ ቀመሰ፣ ወይን ጠጅው ከየት እንደ መጣ አላወቀም፣ ስለዚህ የግብዣው ኀላፊ ሙሽራውን ጠርቶ እንዲህ አለው፣**

10. **"ሰው ሁሉ አስቀድሞ የሚያቀርበው ጥሩውን የወይን ጠጅ ነው፣ እንግዶቹም ብዙ ከጠጡ በኋላ መናኛውን የወይን ጠጅ ያቀርባል፣ ነገር ግን አንተ ጥሩውን የወይን ጠጅ እስከ አሁን አቈይተሃል"**

11. **ኢየሱስ ይህን የምልክቶች መጀመሪያ በገሊላ ቃና አደረገ፤ ክብሩንም ገለጠ፣ ደቀ መዛሙርቱም በእርሱ አመኑ።**

**ቁ.** 1−4 **ኢየሱስ በዮሐንስ ወንጌል "የእኔ ሰዓት" ሲል በመስቀል ላይ ሲሞት ከእግዚአብሔር የሚቀበለው ክብር ማለት ነው። ይህ በሦስተኛ ቀን የተባለው የኢየሱስ ክርስቶስ የትንሣኤን ቀን የሚያስታውስ ነው። የኢየሱስ የመጀመሪያ ተአምራት የሚገልጸው በመስቀሉ ሥራና በትንሣኤ በኩል ለእኛ እውነተኛ እረፍትና ብዙ ሕይወት**

መስጠቱን ነው። ኢየሱስ በመስቀል ላይ የፈጸመው ለእኛ መዳንን ስላስገኘልን እግዚአብሔርን እናመሰግናለን።

**ቁ**. 3-6-10 ኢየሱስ ውሃን ወደ ወይን ጠጅ ለወጠ። ኢየሱስ የሕይወታችንን ጉድለት ወደ ደስታ ሊለውጥና ወደ ጐዶሎ ሕይወታችን እንደ ሠርግ ሥነ ሥርዓት በመምጣት ሕይወታችንን ቀይሮ አዲስ ዘመንን ይከፍታል።

- እኛ ደግሞ ልንለወጥ የጌታን ሥራ እንናፍቃለን።

**ቁ**. 5-7-8 ኢየሱስ የተናገረውን ማርያምና አገልጋዮቹ ታዘዙ። እኛ ደግሞ ለእግዚአብሔር ቃል ከታዘዝን በረከትን እንቀበላለን። እኛ የእግዚአብሔርን ዕቅድና ጊዜን አናውቅም። ነገር ግን መነጫነጫችንን ትተን የተሻለውን እያደረግን የእግዚአብሔርን ፈቃድ በመታዘዝ ልንኖር ያስፈልጋል።

**እንጸልይ**- ጌታ ሆይ! ነፍሳችን ከአንተ አዲስ ወይን ጠጅን ስለተቀበለ ይህን ለሌሎች በደስታ እንድናካፍልና እንድንሰብክ እርዳን።

1. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ

2. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት

3. እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?

4. የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና

5. ትምህርት

6. ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)

7. ፀሎት

6. **የንባብ ክፍል    ዮሐንስ 2፥12-22 ወር፡    ቀን፡**

**ርዕስ፡- ይህ የኢየሱስ ቤተ መቅደስ ነው**

12. ከዚህ በኋላ ኢየሱስ ከእናቱና ከወንድሞቹ፣ ከደቀ መዛሙርቱም ጋር ወደ ቅፍርናሆም ወረደ፣ በዚያም ጥቂት ቀኖች ተቀመጡ።

13. የአይሁድ ፋሲካ በዓል ቀርቦ ስለ ነበር ኢየሱሱ ወደ ኢየሩሳሌም ሄደ፣

14. ኢየሱስ በመቅደስም በሬዎችን፣ በጎችንና ርግቦችን የሚሸጡትንና ገንዘብ ለዋጮችን ተቀምጠው ስዎች አገኘ፤

15. በዚህ ጊዜ ኢየሱስ የገመድ ጅራፍ አበጅቶ በጎችንም በሬዎችንም ከመቅደስ ሁሉ አስወጣቸው፣ የለዋጮችንም ገንዘብ በተነ፣ ጠረጴዞቻቸውንም ገለበጠ።

16. ኢየሱስ ለርግብ የሚሸጡትን ሰዎች እንዲህ አላቸው፤ "ይህን ሁሉ ከዚህ ውሰዱ! የአባቴን ቤት የንግድ ቤት አታድርጉት!"

17. በዚህ ጊዜ ደቀ መዛሙርቱ፤ "ስለቤትህ ያለኝ ቅናት እንደ እሳት አቃጠለኝ" ተብሎ እንደ ተጻፈ አስታወሱ።

18. ከዚህ በኋላ አይሁድ ለኢየሱስ እንዲህ አሉት። "አንተ ይህን ለማድረግ ሥልጣን እንዳለህ ምን ተአምር ታሳየናለህ?"

19. ኢየሱስም እንዲህ መለሰላቸው። "ይህን ቤተ መቅደስ አፍርሱት፣ እኔም በሦስት ቀን መልሼ አነሣዋለሁ"

20. ስለዚህ አይሁድ እንዲህ አሉት። "ይህን ቤተ መቅደስ ለመሥራት አርባ ስድስት ዓመት ፈጅቶአል፣ ታዲያ አንተ እንዴት በሦስት ቀን ውስጥ ታነሣዋለህ?"

21. ነገር ግን ኢየሱስ "ቤተ መቅደስ" ብሎ የተናገረውን ስለ ሰውነቱ ነበር።

22. ስለዚህ ኢየሱስ ከሞት በተነሣ ጊዜ ደቀ መዛሙርቱ ይህን ተናግሮ እንደ ነበረ አስታወሱ፤ በዚህ ምክንያት በቅዱስ መጽሐፍ የተጻፈውንና ኢየሱስ የተናገረውን ቃል አመኑ።

**ቁ.15**  ኢየሱስ ለቤተ መቅደስ ተግባሩንና ችሎታውን ሊመልስ መጣ። የአይሁድ መሪዎች የተቀደሰ መቅደሱን የንግድ ቦታ አደረጉት። ነገር ግን ኢየሱስ ይህን አይቶ እጅግ ተቆጣ።

- ዛሬ ኢየሱስ በልባችን ውስጥ ያለውን የእግዚአብሔርን ቤተ መቅደስ አይቶ ምን ብሎ ያስባል?

**ቁ**.19−22 በሦስተኛ ቀን ቤተ መቅደስን ጠገነ ማለት ኢየሱስ በሦስተኛ ቀን ከሞት እንደሚነሣ የሚገልጽ ማለት ነው። እኛ ጌታ ኢየሱስ ክርስቶስን ብናምን ኢየሱስ በቤተ መቅደሱ ይሆናል። ስለዚህ እኛ በኢየሱስ ክርስቶስ ኅብረት ውስጥ አለን?

**ቁ**.14 ለእግዚአብሔር ክብር የተሰጠው ዕቃ ውሎ አድሮ የሰውን ሥሥት ለማጥገብ የተሠራ መሣሪያ ሆነ። በቤተክርስቲያን ውስጥ በምቾትና በድሎት የሚደረጉ ነገሮች እኛን ያለ እምነት የሚመሩ አይደሉምን?

**ቁ**. 16 ቤተ መቅደስ ለእግዚአብሔር የፀሎት ቦታ ነው። ቤተክርስቲያን ትርፍን የሚያገኙበት ቦታ አይደለም።

**ቁ**. 18 አይሁዶች ስለእግዚአብሔር ቤት የኢየሱስ ቅዱስ ምኞትን አልተጠነቀቁም። ነገር ግን ተአምራዊ ምልክቶችን ብቻ ይጠይቃሉ። እኛ በሕይወታችን ማንን ተስፋ አደረግን?

**እንጸልይ**፦ ጌታ ሆይ! እኛ እንደገና እንደ ኢየሱስ ክርስቶስ የእግዚአብሔርን ቤት እንድንረዳ ምኞትን በውስጣችን አኑረን፤ አሜን።

1. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ

2. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት

3. እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?

4. የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና

5. ትምህርት

6. ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)

7. ፀሎት

7. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 2፥23−3፥15 **ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፡− እኛ በመንፈስ ቅዱስ በኩል እንደገና ተወልድን**

**ዮሐንስ** 2፥ 23. **ኢየሱስ በፋሲካ በዓል በኢየሩሳሌም ሳለ፣ ብዙ ሰዎች ያደረገውን ምልክቶች አይተው በእርሱ አመኑ፣**

24. **ነገር ግን ኢየሱስ ሰውን ሁሉ ስለሚያውቅ፣ ራሱን ለእነርሱ አይታመንባቸውም ነበር፣**

25. **ኢየሱስ በሰው ልብ ያለውን ሁሉ ያውቅ ስለ ነበር፣ ስለ ሰው ማንም እንዲመሰክርለት አያስፈልገውም ነበር።**

**ዮሐንስ** 3፥ 1. **ኒቆዲሞስ የሚባል አንድ ሰው ነበረ፣ እርሱ ከፈሪሳውያን ወገን የሆነ የአይሁድ አለቃ ነበረ።**

2. **ኒቆዲሞስም በሌሊት ወደ ኢየሱስ መጥቶ እንዲህ አለው። “መምህር ሆይ፣ እግዚአብሔር ከእርሱ ጋር ካልሆነ በቀር እነዚህን አንተ የምታደርጋቸውን ተአምራት ሊያደርግ የሚችል ማንም የለም፣ ስለዚህ አንተ ከእግዚአብሔር ዘንድ የመጣህ መምህር እንደ መሆን እናውቃለን”**

3. **ኢየሱስም መልሶ እንዲህ አለው። “እኔ በእውነት እልሃለሁ፣ ሰው ዳግመኛ ካልተወለደ በቀር የእግዚአብሔርን መንግሥት ሊያይ አይችልም”**

4. **ኒቆዲሞስም ለኢየሱስ እንዲህ ጠየቀ። “ታዲያ፣ ሰው ከሸመገለ በኋላ እንዴት ሊወለድ ይችላል**? **ዳግመኛ ወደ እናቱ ማሕፀን ገብቶ መወለድ ይችላል**?”

5. **ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰ፣ “እኔ በእውነት እልሃለሁ፣ ማንም ከውሃና ከመንፈስ ቅዱስ ካልተወለደ በቀር ወደ እግዚአብሔር መንግሥት ሊገባ አይችልም።**

6. **ከሥጋ የተወለደ ሥጋ ነው፣ ከመንፈስ የተወለደ መንፈስ ነው።**

7. **ስለዚህ** ‘**ዳግመኛ መወለድ ያስፈልጋችኋል**’ **ስላልኩህ አታድንቅ።**

8. **ነፋስ ወደሚወደው ይነፍሳል፣ ነገር ግን ከየት እንደሚመጣና ወዴትም እንደሚሄድ አታውቅም፣ ከመንፈስ የተወለደ ሁሉ እንዲሁ ነው።**

9. **ኒቆዲሞስም ለኢየሱስ እንዲህ ሲል ጠየቀው፣ “ይህ እንዴት ሊሆን ይችላል**?”

10. **ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰለት፣ “አንተ የእስራኤል መምህር ሆነህ ሳለ እነዚህን ነገሮች አታውቅምን**?”

11. **እኔ በእውነት እልሃለሁ፣ እኛ የምናውቀውን እንናገራለን፣ ያየነውንም እንመሰክራለን፣ ነገር ግን እናንተ ምስክርነታችንን አትቀበሉትም።**

12. እኔ ለእናንተ ስለ ምድራዊ ነገር በነገርኋችሁ ጊዜ ካላመናችሁ፣ ስለ ሰማያዊ ነገር ብነግራችሁ እንዴት ታምናላችሁ?
13. ከሰማይ ከወረደው ከሰው ልጅ በቀር፣ ወደ ሰማይ የወጣ ማንም የለም።
14. ሙሴ በምድረ በዳ እባብን እንደ ሰቀለ፣ የሰው ልጅም እንዲሁ ሊሰቀል ይገባዋል፣
15. ይህም በኢየሱስ የሚያምን ሁሉ የዘለዓለምን ሕይወት እንዲያገኝ ነው።

**ቁ. ምዕ.** 3፥13−15 በብሉይ ኪዳን ጊዜ በምድረ በዳ ሙሴ የናስ እባብ ሠርቶ በረጅም በትር ላይ ሰቀለ። የእስራኤላዊያን ሕዝብ የተሰቀለውን የናስ እባብ በመመልከት ከሞት ዳኑ። ስለዚህ የእኛ ኃጥአት ይቅር ስለተባለ በአንድ መንገድ ኢየሱስ ክርስቶስን ተመልክተን የዘላለም ሕይወትን ተቀበልን።

**ቁ.** 3፥3−5 የአይሁድ መሪ የሆነው ኒቆዲሞስ በሌሊት ኢየሱስን እየፈለገ መጣ። ኒቆዲሞስ ሰው ከመንፈስ ቅዱስ እንደገና እንደሚወለድ አልተገነዘበም። “እንደገና መወለድ” ማለት ከላይ መወለድ ማለት ነው። ይህ ከላይ ተወለደ ሲል ከምድርና ከተፈጥሮ ተወለደ ማለት አይደለም። ነገር ግን ከውሃና ከመንፈስ ቅዱስ ከእግዚአብሔር አዲስ ተወለደ ማለት ነው። ኒቆዲሞስ በጣም የሚያስፈልግ ሰው ነው። ነገር ግን እርሱ ከመንፈስ ቅዱስ እንደገና ስላላተወለደ ምንም የማያውቅ ሰው ነው። እንዲህ የከፍተኛ ማህበራዊ ሹመት ያለው ሰው ቢሆን ዝቅተኛ የማህበራዊ ሹመት ያለው ሰው ባይሆንም የመጽሐፍትን ዕውቀት በብዛት የሚያውቅ ሰው ቢሆንም እንዲሁም የማያውቅ ሰው ቢሆን እንደገና ከመንፈስ ቅዱስ መወለድ አስፈላጊ ነው። ብቻ እኛ የምንጸልየው ሰው ሁሉ ከመንፈስ ቅዱስ እንደገና እንዲወለድ ነው።

**ምዕ.** 3፥6 መንፈሳዊ ልደትን በሰው ጥረት ማግኘት አይቻልም። (1፥13) በዓለም ላይ እኛ ጸንተን የመኖራችን ጉዳይ ምንም አይደለም። እኛ የኢየሱስ ክርስቶስ የቤዛነትን ሥራ አንቀበልም ብንል የእኛ መጨረሻ ፍርድና ሞት ይሆናል። **እንጸልይ፦** ጌታ ሆይ! በመንፈስ ቅዱስ ሥራ በኩል እኛ ኢየሱስን እንድንቀበል ስለፈቀድክልን እናመሰግናለን፤ አሜን።

1. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ

2. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት

3. እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?

4. የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና

5. ትምህርት

6. ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)

7. ፀሎት

**8. የንባብ ክፍል ዮሐንስ 3፥16-21 ወር፦ ቀን፦**

**ርዕስ፦- እግዚአብሔር ዓለምን በፈቃዱ ወደደ**

16. እግዚአብሔር ዓለምን እጅግ ሰለ ወደደው አንድያ ልጁን ሰጠ፤ ይህ በኢየሱስ የሚያምን ሁሉ እንጂ እንዳይጠፋ የዘላለም ሕይወት እንዲኖረው።

17. እግዚአብሔር ልጁን ወደ ዓለም የላከው፤ በዓለም እንዲፈርድ ሳይሆን፤ ዓለምን በኢየሱስ ለማዳን ነው።

18. በኢየሱስ የሚያምን ሁሉ አይፈረድበትም፤ ነገር ግን በኢየሱስ የማያምን በአንዱ በእግዚአብሔር ልጅ ስም ስላላመነ፤ ቀድሞውኑ ተፈርዶበታል።

19. ፍርዱም ይህ ነው፤ ብርሃን ወደ ዓለም መጣ፤ ሰዎች ግን ሥራቸው ክፉ ስለ ነበረ፤ ከብርሃን ይልቅ ጨለማን ወደዱ፤

20. ክፉ ነገር የሚያደርግ ሁሉ ብርሃንን ይጠላል፤ ክፉ ሥራውም እንዳይገለጥበት ወደ ብርሃን አይመጣም።

21. ነገር ግን እውነትን የሚያደርግ ሥራው ወደ ብርሃን ይመጣል፤ ወደ ብርሃን የሚመጣውም ያደረገው ነገር በእግዝአብሔር ትእዛዝ መሠረት መሆኑ በግልጽ እንዲታይ ነው።

ቁ.16-17 እግዚአብሔር ለዓለም በጣም የሚወደውን ኢየሱስን ለመስቀል ሞት በመስጠቱ ፍቅሩን አሳየ። ይህ ፍቅር ለሁሉ ወገን እውነተኛ የምሥራች ነው። ስለዚህ እኛ ኢየሱስን ተቀብለናል?

ቁ. 18 ኢየሱስ ክርስቶስን የማያምኑ ሰዎች ቀድሞም የተፈረዱ ናቸው። ይህ ማለት ሌላ ፍርድ አስፈላጊ አይደለም። ምክንያቱም የዘላለም ሕይወት ደስታ ስላላተቀበሉ በመጀመሪያም የተፈረዱ ናቸው። እኛ በዓለም በነፃነት እንደሰታለን። ነገር ግን የኢየሱስ ክርስቶስ ስም የማያምኑ ሰዎች አሁን እንኳ ከፍርድ በታች መሆናቸውን ያስታውሳል።

ቁ. 18-21 ዳግመኛ ያልተወለዱ ሰዎች ኃጢአተኞች ስለሆኑ ከእግዚአብሔር ጋር ያላቸው ግንኙነት የመቋረጥ ውጤት ፍርድ ነው። እግዚአብሔር ለሰዎች በኢየሱስ

ስም እንዲያምኑ ደኅንነትን ሰጠ። ነገር ግን ይህ ሥርዓትን ላልተቀበሉ የዘላለም ፍርድ ይሆናል። እኛ ከጨለማ የተነሣ ለእግዚአብሔር ልቦናችንን ዘግተናል?

**ቁ**. 19-21 *የማያምኑ ሰዎች በመጀመሪያም የተፈረዱ ናቸው። እነርሱ ጨለማ ዓለምን ወድደው ወደ ኢየሱስ ብርሃን አልመጡምና። ነገር ግን የሚያምኑ ሰዎች በሕይወታቸው የዚህ ብርሃን ፍሬ ያፈራሉ። ታዲያ እኛ በየቀኑ በዚህ ብርሃን መካከል እየሄድን የብርሃንን ፍሬ ብዙ አፈራን?*

**እንጸልይ፡-** *ጌታ ሆይ! እኛን ወድደህ ኢየሱስ ክርስቶስን ስለሰጠኸን ስለ ፀጋህንም ስለላክ እናመሰግናለን፤ አሜን።*

1. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ

2. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት

3. እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?

4. የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና

5. ትምህርት

6. ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)

7. ፀሎት

9. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ 3፥22-36 ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፦ የመጥምቁ ዮሐንስ የመጨረሻ ምስክርነት**

22. ከዚህ በኋላ ኢየሱስ ከደቀ መዛሙርቱ ጋር ወደ ይሁዳ አገር ሄደ፤ እዚያም ከእነርሱ ጋር ጥቂት ተቀመጠ፤ አጠመቀም።

23. በዚህ ጊዜ ዮሐነስም በሳሌም አቅራቢያ ሄኖን በተባለ ስፍራ ብዙ ውሃ ስለ ነበረ፤ ያጠምቀነበር፤ ሰዎችም እየመጡ ይጠመቁ ነበር።

24. ይህም ዮሐንስ ገና ወደ ወኅኒ ከመታሰሩ በፊት ነበር።

25. በዚያን ጊዜ በአንዳንዱ የዮሐንስ ደቀ መዛሙርትና በአንድ አይሁዳዊ መካከል ስለ መንጻት ሥርዓት ክርክር ተነሣ፤

26. የዮሐንስ ደቀ መዛሙርት ወደ ዮሐንስ ቀርበው እንዲህ አሉት። "መምህር ሆይ፤ ያ ከዮርዳኖስ ማዶ ከአንተ ጋር የነበረው፣ አንተ ስለ እርሱ የመሰከርክለት፣ እነሆ፣ እርሱም ያጠምቃል፤ ሰዎችም ሁሉ ወደ እርሱ እየሄደ ነው"

27. ዮሐነስም እንዲህ ሲል መለሰ፤ እግዚአብሔር ካልተሰጠው በቀር ማንም አንዳች ሊቀበል አይችልም።

28. 'እኔ ክርስቶስ አይደለሁም፤ ነገር ግን ከእርሱ በፊት ተልኬአለሁ' እንዳልሁ እናንተ ራሳችሁ ትመሰክራላችሁ።

29. ሙሽሪት ያለችው ሰው ሙሽራ ነው፤ ነገር ግን የሙሽራው ሚዜ ከሙሽራው አጠገብ ቆሞ ይሰማዋል፤ የእርሱንም ድምፅ ሲሰማ እጅግ ይደሰታል፤ ስለዚህ የእኔም ደስታ አሁን ተፈጽሞአል።

30. ኢየሱስ ሊልቅ፤ ነገር ግን እኔ ላንስ ይገባል።

31. ከላይ የሚመጣው ከሁሉ በላይ ነው፤ ከምድር የሚሆነው የምድር ነው፤ የምድሩንም ይናገራል። ከሰማይ የሚመጣው ከሁሉ በላይ ነው።

32. ኢየሱስ ያየውንና የሰማውን ይመሰክራል፤ ነገር ግን የኢየሱስን ምስክርነት የሚቀበል የለም።

33. የኢየሱስን ምስክርነት የተቀበለ ሰው፣ እግዚአብሔር እውነተኛ መሆኑን ያረጋግጣል።

34. እግዚአብሔር የላከው የእግዚአብሔርን ቃል ይናገራልና፤ እግዚአብሔር መንፈሱን ለኢየሱስ ሳይሰፍር ስለሚሰጥው።

35. አብ ልጁን ይወዳል፤ ሁሉንም ነገር በእጁ ሰጥቶታል።

36. በልጁ የሚያምን ሁሉ የዘላለም ሕይወት አለው፤ ነገር ግን በልጁ የማያምን የእግዚአብሔር ቍጣ በእርሱ ላይ ይኖራል እንጂ ሕይወትን አያገኝም።

**ቁ.**32-33  ኢየሱስ የእውነት ምንጭ ነው። ምክንያቱም ኢየሱስ ሁልጊዜ የእግዚአብሔርን ቃል ስለሚናገር ነው። ስለዚህ የእግዚአብሔርን ቃል የተቀበለ ሰው ለእግዚአብሔር ጽድቅ ማስረጃ ነው። እኛ የእግዚአብሔር ቃል እንዴት አደረግን?

**ቁ.** 34  ኢየሱስ የእግዚአብሔርን ቃል ሳያቋርጥ ተናገረ። ምክንያቱም እግዚአብሔር ለኢየሱስ መንፈስ ቅዱስን ሳያቋርጥ ሰጥቷልና። የኢየሱስ ቃል በመንፈስ ቅዱስ የተሞላ ስለሆነ ዛሬ በእኛም መንፈስ ቅዱስ እንዲሞላን እንጸልያለን።

**ቁ.** 35-36  ኢየሱስ ለሚያምኑ ሰዎች የዘላለምን ሕይወት ይሰጣል። ነገር ግን እርሱን ለማያምኑ ሰዎች የዘላለም ፍርድ ይሰጣል። እኛ የዘላለምን ሕይወት የምናገኝበትን ብቸኛው መንገድ ኢየሱስን አመንን! ነገር ግን ኢየሱስን ለማይቀበሉ የእግዚአብሔር ፍርድ በእነርሱ ላይ ይሆናል።

**ቁ.** 25-26  መጥምቁ ዮሐንስ ሰዎች እየተጠመቁ ወደ ኢየሱስ ሲሄዱ ባየ ጊዜ የኢየሱስን አገልግሎት ለእነርሱ አስታወቃቸው።

- ሌሎች ሰዎች ከእኛ ይልቅ ብዙ ሥራ ሲያከናውኑ ምን ይሰማናል? እኛ ሌሎች ሰዎችን አንቀናባቸውም። ምክንያቱም የሥራ ውጤታቸውን የሚሰጠው እግዚአብሔር ነውና።

**ቁ.** 27-30  መጥምቁ ዮሐንስ ችሎታው ውስን መሆኑን አወቀ። ስለዚህ ዮሐንስ የአንድ ሥርግ ልብስ ወዳጅ/ሚዜ/ ነው። ሚስቱን ወደ ልብሱ/ወደ ኢየሱስ/ በመምራቱ ይደሰታል። ይህ ማለት ዮሐንስ ክርስቲያኖችን ወይም እኛን ለኢየሱስ በማስረከቡ ተደስቷል ማለት ነው። ዛሬ በሕይወታችን ጌታ ከፍ ብሎ እኛ ዝቅ ልንል ያስፈልጋል።

**እንጸልይ፦** ጌታ ሆይ! በሕይወታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከፍ ብሎና እኛም ለክብሩ ዝቅ ብለን እውነትን ሁልጊዜ በመያዝ ለዘላለም እንድንኖር እርዳን፤ አሜን።

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

## 10. የንባብ ክፍል ዮሐንስ 4፥1−14 ወር፡ ቀን፡

## ርዕስ፡− ኢየሱስ ከሰማርያ ሴት ጋር ተገናኘ

1. በዚያን ጊዜ ኢየሱስ ከዮሐንስ ይበልጥ ብዙ ሰዎችን ደቀ መዛሙርት እንደሚያደርግ እንደሚያጠምቅ ፈሪሳውያን ሰሙ፣

2. ኢየሱስ ራሱ አያጠምቅም ነበር፤ ነገር ግን የእርሱ ደቀ መዛሙርት ይጠመቁ።

3. ኢየሱስም ይህን እንዳወቀ የይሁዳን ምድር ትቶ ወደ ገሊላ ተመልሶ ሄደ።

4. ኢየሱስም በሰማርያ በኩል ማለፍ ነበረበት።

5. ስለዚህ ኢየሱስ ሲካር ወደምትባል የሰማርያ ከተማ መጣ። ይህ ከተማ የያዕቆብ ለልጁ ለዮሴፍ በሰጠው ቦታ አጠገብ ወደ ነበረች፣

6. በዚያም የያዕቆብ የውሃ ጉድጓድ ነበረ፣ ኢየሱስም ከጉዞው የተነሣ ስለ ደከመው በውሃው ጉድጓድ አጠገብ ተቀመጠ፣ ጊዜውም ከቀኑ ስድስት ሰዓት ያህል ነበር።

7. በዚያን ጊዜ አንዲት የሰማርያ አገር ሴት ውሃ ልትቀዳ ወደ ጉድጓዱ መጣች፣ ኢየሱስም "ውሃ አጠጪኝ!" አላት።

8. በዚያን ወቅት ደቀ መዛሙርቱ ምግብ ሊገዙ ወደ ከተማ ሄደው ነበር።

9. ሳምራዊት ሴት ለኢየሱስ እንዲህ አለችው፣ "አንተ አይሁዳዊ ሆነህ፣ እኔን ሳምራዊቷን እንዴት ውሃ አጠጪኝ" ትላለህ?" ይህን ማለትዋ፣ አይሁድ ከሳምራውያን ጋር ስለማይተባበሩ ነው።

10. ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰላት። "የእግዚአብሔር ስጦታና 'ውሃ አጠጪኝ!' የሚልሽ ማን እንደ ሆነ ብታውቂው ኖሮ፣ አንቺ ለእርሱ በጠየቅሽው፣ እርሱም የሕይወትን ውሃ ይሰጥሽ ነበር"

11. ሴቲቱም እንዲህ አለችው፣ "ጌታ ሆይ! አንተ መቅጃ የለህም፣ ጉድጓዱም ጥልቅ ነው፣ ታዲያ፣ የሕይወት ውሃ ከየት ታገኛለህ?

12. አንተ ይህን ጉድጓድ ከሰጠን ከአባታችን ከያዕቆብ ትበልጣለህን? እርሱና ልጆቹ፣ ከብቶቹም ከዚህ ጉድጓድ ጠጥተዋል።"

13. ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰላት፣ "ከዚህ ውሃ የሚጠጣ ሁሉ እንደገና ይጠማል፣

14. ነገር ግን እኔ ከምሰጠው ውሃ የሚጠጣ ለዘለዓለም ከቶ አይጠማም፣ እኔ የምሰጠው ውሃ በእርሱ ውስጥ ለዘለዓለም ሕይወት የሚፈልቅ የውሃ ምንጭ ይሆናል።"

ቁ. 3−4 ኢየሱስ የሰማርያ ሴትና ሌሎችን ከመውደዱ የተነሣ በሰማርያ መንገድ ሄደ። እኛ እንደ ኢየሱስ ክርስቶስ ወደ ሌሎች ሰዎች ሄደናል?

ቁ. 6 ኢየሱስ ከረጅም ጉዞ በኋላ እጅግ ደክሞ ነበር። የተከበረ እግዚአብሔር "ወደ እኛ መጥቶ ከእኛ ጋር የሚኖር" ይህን ስል ኢየሱስ እንደ እኛ ድካም፣ ረሃብ፣ ሐዘን፣ ብቸኝነት ተሰምቶታል ማለት ነው። ኢየሱስ ሰው እንደ ሚያዝን ያዝናል፤ ሰውም እንደሚያስብ ያስባል።

ቁ. 7−9 ኢየሱስ ከሁሉ ሰዎች አድሎዎን ማህበራዊ ሥርዓትንና የሃይማኖተኛነት ሥርዓት ሰበረ። አይሁድ የነበረው ኢየሱስ ለሰማርያ ሴት እንደተናገረ በዚያን ጊዜ ሰዎች በእውነተኛ መገረም ተገርመው ነበር። ነገር ግን ኢየሱስ ያንን ግንብ ሰብሮ ሁሉንም አንድ ለማድረግ መጣ።

ቁ. 10−14 ኢየሱስ ለእኛ የዘላለም ሕይወት ውሃ ምንጭ ሰጠ። የያዕቆብ የውሃ ጉድጓድ የሕዝብን ጥማት ለዘላለም አያጠፋም። ነገር ግን ኢየሱስ ለእኛ ለዘላለም የሚሆን የሕይወት ውሃ ሰጠን። ስለዚህ ወደ ሕያው ውሃ/ኢየሱስ/ እንምጣ!

ቁ. 12 የሰማርያ ሴት ኢየሱስ የተናገረላትን ውሃ ምን እንደሆነ አላወቀችም። ብቻ የእርሱን የተፈጥሮ ውሃ ምንጭ ታውቃለች። ነገር ግን ውሃ ማለት የዘላለም ሕይወት ውሃ ያም ኢየሱስ ነው። እንደዚሁም ኒቆዲሞስ አላወቀም። እኛ የእግዚአብሔርን ነገር ለማስተዋል የመንፈስ ቅዱስ ርዳታ ያስፈልገናል። (14፡26)

**እንጸልይ፡- ጌታ ሆይ! ለእኛ የሕይወት ውሃ ፈቅዶ ስለሰጠን እግዚአብሔርን እናመሰግናለን። እኛም ይህንን የዘላለም ውሃ ምንጭ የሆነውን ኢየሱስን ለሌሎች እንድንሰብክ እርዳን፤ አሜን።**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

## 11. የንባብ ክፍል ዮሐንስ 4፥15−26 ወር፡ ቀን፡

### ርዕስ፡− በእውነትና በመንፈስ አምልኩ!

15. ሴቲቱም እንዲህ አለችው፣ "ጌታ ሆይ! እባክህ እንዲህ ዓይነቱን ውሃ ስጠኝ! እንዳይጠማኝና ወደዚህም ለመቅዳት እንዳልመጣ አደርጋለሁ።" 16. ኢየሱስም እንዲህ አላት። "ሂጂና ባልሽን ጠርተሽ ወደዚህ ተመለሽ"

17. ሴቲቱም እንዲህ ብላ መለሰች። "ባል የለኝም" በዚህ ጊዜ ኢየሱስ እንዲህ አላት፣ "ባል የለኝም ማለትሽ ትክክል ነው።" 18. በእርግጥ አምስት ባሎች ነበሩሽ፣ አሁንም ከአንቺ ጋር ያለው ሰው ባልሽ አይደለም፣ ስለዚህ የተናገርሽው እውነት ነው። 19. ሴቲቱ እንዲህ አለችው፣ "ጌታ ሆይ! አንተ ነቢይ እንደ ሆንህ አያለሁ፣

20. አባቶቻችን በዚሁ ተራራ ላይ ሰገዱ፣ ነገር ግን እናንተ 'አይሁድ ሰዎች ሊሰግዱ የሚገባቸው በኢየሩሳሌም ነው' ትላላችሁ።" 21. ኢየሱስም እንዲህ አላት፣ "አንቺ ሴት፣ እመኚኝ፣ በዚህ ተራራ ወይም በኢየሩሳሌም ለአብ የማትሰግዱበት ጊዜ ይመጣል። 22. እናንተ ሳምራውያን ለማታውቁት ትሰግዳላችሁ፣ ነገር ግን እኛ ለምናውቀው እንሰግዳለን፣ ይህ መዳን ከአይሁድ ስለ ሆነ።

23. ነገረ ግን በእውነት የሚሰግዱ፣ ለአብ በመንፈስና በእውነት የሚሰግዱበት ጊዜ ይመጣል፣ አሁንም መጥቶአል፣ አብም እንደዚህ በእውነት የሚሰግዱለትን ይፈልጋል። 24. እግዚአብሔር መንፈስ ነው፣ ለእግዚአብሔር የሚሰግዱለትም በመንፈስና በእውነት ሊሰግዱለት ይገባቸዋል።

25. ሴቲቱም እንዲህ አለችው፣ "ነኝ ክርስቶስ የሚባል ክርስቶስ እንደሚመጣ አውቃለሁ፣ እርሱ ሲመጣ ሁሉን ነገር ይነግረናል" 26. ኢየሱስም እንዲህ አላት፣ "አሁን የማነጋግርሽ እኔ እርሱ ነኝ"

**ቁ**. 15−18 ኢየሱስ ለሕይወታችን መሠረታዊ የሆነው ጥማትን የሚገልጽና ለችግሮቻችን መፍትሔ የሚሰጥ ጌታ ነው። ኢየሱስ ከጉድጓድ ውሃ ወደ ምትቀዳ ሴት መጥቶ እርስዋ ባልዋን ይዛ እንድትመጣ ነገራት። "ባልሽን ሄደሽ አምጭ" ማለት እርስዋ አስቀድማ ኃጢአትዋን መናዘዝ ማለት ነው።

**ቁ**. 21−22 ኢየሱስ የመጀመሪያውን ቤት መቅደስ ተክቶ በሰው ልብ ውስጥ አዲስ ቤት መቅደስን አመጣ። ስለዚህ እኛ ስለ አምልኮ ቦታዎች መጨነቅ

አያስፈልግም። በሁሉ ሥፍራ ያለው ኢየሱስ ስለሆነ እኛ ሁልጊዜ ወደ እግዚአብሔር በመሄድ የሕይወትን ውሃ መጠጣት እንችላለን።

**ቁ**. 23−24 ኢየሱስ በመንፈስና በእውነት እግዚአብሔርን እንድናመልክ መንገዱን ከፈተ። እኛ በእውነተኛ ልብ እግዚአብሔርን ማምለክ እንችላለን። "በመንፈስና በእውነት" ማለት ኢየሱስ ክርስቶስን እንደ ጌታና እንደ ንጉሥ አምኖ በመቀበል ማምለክ ማለት ነው። እግዚአብሔር ዛሬ የኒቆዲሞስ ዓይነት ሰዎች ቢሆኑ የሰማርያ ሴት ዓይነት ሰዎች ቢሆኑም ሁሉም ኢየሱስን እንዲያመልኩ ይፈልጋል።

**ቁ**. 25−26 ኢየሱስ ለሰማርያ ሴት "እኔ አንቺን የማነጋግርሽ እኔ እርሱ ነኝ ብሎ በመናገር ራሱ መሲሕ ስለሆነ ቃሉን ሰብኮ ለኃጢአት የሞቱትን ሰዎች አድኖ አዲስ እስራኤልን ገነባ።

**እንጸልይ፦** ጌታ ሆይ! እኛ በጉድጓድ ውሃ መመካታችንን አቁመን የዘላለምን ሕይወት ውሃ ምንጭ ኢየሱስን በመቀበል እርሱንም እንድናመልክ እርዳን፤ አሜን።

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

12. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 4፥27-42 **ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፡- የሕይወትን ውሃ የጠጣችው ሴት ሕይወት**

27. **በዚህ ጊዜ ደቀ መዛሙርቱ ከሄዱበት ተመልሰው መጡ፣ ኢየሱስ ከሴት ጋር በመነጋገሩ ተደነቁ፣ ነገር ግን "ምን ትፈልጋለህ? ወይመ ከእርስዋ ጋር ለምን ትነጋገራለህ?" ብሎ የጠየቀው ማንም አልነበረም።**

28. **ከዚህ በኋላ ሴቲቱ እንስራዋን ትታ ወደ ከተማ ሄደችና ለሰዎቹ እንዲህ አለች፣**

29. **"ያደረግሁትን ሁሉ የነገረኝን ሰው ኑና እዩ፣ ምናልባት እርሱ ክርስቶስ ይሆንን?"**

30. **ሰዎቹም ከከተማ ወጥተው ወደ ኢየሱስ ይመጡ ነበር።**

31. **በዚህ ጊዜ ደቀ መዛሙርቱ ለኢየሱስ እንዲህ ሲሉ ለመኑት። "መምህር ሆይ! አንዳች ምግብ ብላ"**

32. **ነገር ግን ኢየሱስ እንዲህ አላቸው። "እናንተ የማታውቁት እኔ የምበላው ምግብ አለኝ"**

33. **ስለዚህ ደቀ መዛሙርቱ እንዲህ ተባባሉ። "አንዳች ሰው ለኢየሱስ ምግብ አምጥቶለት ይሆን?"**

34. **ኢየሱስም እንዲህ አላቸው፣ የእኔ ምግብ የላከኝን ፈቃድ ማድረግና ሥራውን መፈጸም ነው፣**

35. **እናንተ፣ 'ከአራት ወር በኋላ መከር ይደርሳል' ትሉ የለምን? እኔ እንዲህ እላችኋለሁ፣ ዓይናችሁን ከፈቶ እርሻውን ተመልከቱ፣ አሁን አዝመራው እንደ ነጣ ለመከር እንደ ደረሱ ሆነ።**

36. **የሚያጭድ ደመወዝን ይቀበላል፣ ለዘላለም ሕይወት የሚሆን ፍሬም ይሰበስባል፣ ስለዚህ የሚዘራውም፣ የሚያጭደውም አብረው ይደሰታሉ።**

37. **ስለዚህ፣ 'አንዱ ይዘራል፣ ሌላውም ያጭዳል' የተባለው ቃል እውነት ነው።**

38. **እኔም እናንተ ያልደከማችሁበትን እንድታጭዱ ላክኋችሁ፣ ሌሎች በሥራ ደከሙ፣ እናንተም የድካማቸውን ፍሬ ሰበሰባችሁ።"**

39. **ሴቲቱም፣ "ኢየሱስ ያደረግሁትን ሁሉ ነገረኝ" ብላ ስለ መሰከረችው፣ ከዚያች ከተማ ብዙ የሰማርያ ሰዎች ኢየሱስን አመኑ።**

40. **ስለዚህ የሰማርያ አገር ሰዎች ወደ ኢየሱስ በመጡ ጊዜ ከእነርሱ ጋር እንዲቈይ ለመኑት፣ ኢየሱስም ሁለት ቀን እዚያ ቈየ።**

41. **በቃሉም ምክንያት ሌሎች ብዙ ሰዎችም ኢየሱስን አመኑ።**

42. እነርሱ ለሴቲቱ እንዲህ አሉአት። "ከእንግዲህ የምናምነው አንቺ ስለ ነገርሽን ቃል ብቻ አይደለም፣ እኛ ራሳችን ስለ ሰማንና በእርግጥ ኢየሱስ የዓለም አዳኝ እንደ ሆነ ስላወቅን ነው"

ቁ. 31-34 ኢየሱስ የእግዘአብሔርን ፈቃድ አደረገ። ኢየሱስ ወሃን ለመቅዳት ለመጣችው ሴት "በውሃ" በኩል የዘላለምን ሕይወት ገለጸ። ደግሞም "እንጀራ" በማምጣት ለደቀ መዛሙርቱ ሚስዮናዊነታቸውን ገለጸ። እንጀራን በመብላት ሰዎች እንደሚኖሩ እኛ የእግዚአብሔርን ቃል በማንበብ የእኛ መንፈሳዊነታችንን እናኖራለን።

ቁ. 35 ኢየሱስ ለደቀ መዛሙርቱ የመከሩ ሰዓት ቅርብ እንደ ሆነ አሳየ። እኛም እንደ ኢየሱስ ሌሎችን ወደ እግዚአብሔር የምናመጣ ሰዎች መሆን አለብን።

ቁ. 36-38 ወንጌልን ሰብኮ ለሚዘራ ሰውና ለምርቱ ኢየሱስ ደስታውን ሰጣቸው። ከእኛ በፊት ብዙ ታማኝ ምስክሮች የወንጌልን ዘር ዘርተዋል። እኛ ደግሞ ፍሬውን ለመውሰድ አንድከም።

ቁ. 28-29-39 ሴቲቱ ኢየሱስ ከተገናኛት በኋላ የወሃ መቅጃ ማንቆርቆሪያዋን በመጣል ወደ አቅራቢያ ቤት በመሮጥ ስለ ኢየሱስ ለሰዎቹ ሁሉ ተናገረች። ምክንያቱም ሴቲቱ የሕይወትን ወሃ ከኢየሱስ ስለተቀበለች ነው። ሴቲቱ የሕይወትን ወሃ ለመቀበል ከጉድጓድ ወሃ የምትቀዳውን ማንቆርቆሪያ አስፈላጊ አይደለም። ሴቲቱ ኢየሱስን ከመገናኘቷ በፊት በሰዎች ዘንድ የነበራትን ሐፍረት ኢየሱስን ከተገናኘች በኋላ በድፍረት ለወጠችው። እኛ ደግሞ ከኢየሱስ ጋር ከተገናኘን በኋላ በእንደዚህ ዓይነት ለውጥ ተለውጠናል?

**እንጸልይ፡- ጌታ ሆይ! የእግዚአብሔርን ፈቃድ እንድንፈጽም የወንጌልን ዘር እንድንዘራ እርዳን፤ አሜን።**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

13. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 4፥43−54 **ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፡− የኢየሱስ ቃል ለእኛ የዘላለም ሕይወትን ይሰጣል**

43. **ከሁለቱ ቀናት በኋላም ኢየሱስ ከዚያ ወጥቶ ወደ ገሊላ ሄደ፤**

44. **ኢየሱስ ራሱ፣ “ነቢይ በገዛ አገሩ አይከበርም” ብሎ ተናግሮ ነበር።**

45. **ኢየሱስ ወደ ገሊላ በደረሰ ጊዜ የገሊላ ሰዎች በደስታ ተቀበሉት፣ ምክንያቱም፣ እነርሱም በፋሲካ በዓል ወደ ኢየሩሳሌም ሄደው በነበረበት ጊዜ ኢየሱስ በዚያ ያደረገውን ሁሉ አይተው ስለ ነበር ነው።**

46. **ከዚህ በኋላ ኢየሱሱ ውሃውን የወይን ጠጅ ወዳደረገባት ወደ ገሊላ ቃና ዳግመኛ ተመለሰ፣ በቅፍርናሆምም ልጁ የታመመበት አንድ የቤተ መንግሥት ሹም ነበረ።** 47. **ሹሙም ኢየሱስ ከይሁዳ ምድር ወደ ገሊላ መምጣቱን ሰምቶ ወደ ኢየሱስ ሄደ፣ ወደ ቅፍርናሆም መጥቶ በሞት አፋፍ ላይ የነበረውን ልጁን እንዲፈውስለት ለመነው።**

48. **ኢየሱስም እንዲህ አለው። “እናንተ ተአምራትና ድንቅ ነገር ካላያችሁ ከቶ ምንም አታምኑም!”**

49. **ሹሙም እንዲህ አለው። “ጌታ ሆይ! ልጄ ከመሞቱ በፊት እባክህ ውረድ”**

50. **ኢየሱስም፣ “ወደ ቤትህ ሂድ! ልጅህ በሕይወት ይኖራል” አለው። ሰውየው ኢየሱስ የተናገረውን ቃል አምኖ ወደ ቤቱ ሄደ።** 51. **ሹሙም ሲወርድ አገልጋዮቹ በመንገድ ላይ አገኙትና፣ “ልጅህ ድኖአል” ብለው ነገሩት።**

52. **ሹሙም ልጁ በጎ የሆነበትን ሰዓት ጠየቃቸው። አገልጋዮቹም፣ “ትናንትና በሰባት ሰዓት ትኩሳቱ ለቀቀው” አሉት።** 53. **አባቱም ኢየሱስ “ልጅህ በሕይወት ይኖራል” ያለው በዚያኑ ሰዓት እንደ ሆነ አወቀ፤ ስለዚህ እርሱና ቤተሰቡን ሁሉ ኢየሱስ አመኑ።**

54. **ይህም፣ ኢየሱስ ከይሁዳ ወደ ገሊላ መጥቶ ያደረገውን ሁለተኛው ታአምራዊ ምልክት ነው።**

**ቁ**. 46 **ኢየሱስ በቃና ገሊላ ውሃን ወደ ወይን ጠጅ ወደለወጠበት ተመልሶ ሁለተኛ ለአማኙ አዲስ ሕይወት በመስጠት ታአምራትን አሳየ።**

**ቁ**. 50−54 **ኢየሱስ ሹሙ ስለጠየቀው ጠላ። ነገር ግን ኢየሱስ ለሹሙ ቃል ብቻ በመናገሩ የሹሙን ልጅ ፈወሰ። ኢየሱስ ራሱ ወደ ልጁ ሳይሄድ ቃል ብቻ ተናግሮ እንደፈወሰ አይቶ እነርሱ እንዳመኑ ሊያይ ይፈልጋል። ለሰውነታችንና ለመንፈሳችን የሚያስፈልገውን አውቆ የሰጠውን እግዚአብሔርን እናመሰግናለን።**

**ቁ**. 43-45 **ነብይ በአገሩ አይከበርም። ነገር ግን የገሊላ ሰዎች ኢየሱስን ተቀበሉ። ምክንያቱም እነርሱ በኢየሩሳሌም ኢየሱስ የሠራውን ተአምራትን ለማየት ይፈልጋሉ። ዛሬ እኛ ከእግዚብሔር ቃል ሌላ ተአምራት እንጠብቀዋለን**?

**ቁ**. 50 **ሹሙ "ሂድ ልጅህ በሕይወት ይኖራል" ያለውን የኢየሱስን ቃል አመነ። ይህ አስገራሚ እምነት ነው። የእኛ ሕይወትም ለእግዚአብሔር ቃል መታዘዝ ይገባዋል። ዛሬ እግዚአብሔር ለእኛ በቃሉ እንድንኖር ሲናገር እኛ እንዴትስ ታዘዝነው**?

**እንጸልይ፦- ጌታ ሆይ**! **ዛሬ የኢየሱስን ሥልጣን ተለማምደው በአካባቢያችን ያሉ ሰዎች እርሱን እንዲያምኑ እርዳቸው፤ አሜን።**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ**? **ማን ነው**?

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ** (**በስራ ላይ ማዋል**)

7. **ፀሎት**

14. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ 5፥1—18 ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፡— ኢየሱስ 38 ዓመት የሆነውን በሽተኛን ፈወሰ**

1. ከዚህ በኋላ የአይሁድ በዓል ነበረ፣ ኢየሱስም ወደ ኢየሩሳሌም ሄደ።

2. በኢየሩሳሌም በበጎች በር አጠገብ፣ በዕብራይስጥ ቋንቋ ቤተሳይዳ የሚባል አንዲት መጠመቂያ ነበረ፣ በዙሪያውም አምስት መመላለሻዎች ነበሩ።

3. እዚህ በጣም ብዙ በሽተኞች፣ ዕውሮች፣ አንካሶችና ሽባዎች በመተላለፊያዎቹ ተኝተው ነበር። (እነዚህ የውሃውን መንቀሳቀስ ይጠባበቁ ነበር፣

4. አንዳንድ ጊዜ የጌታ መልአክ ወደ መጠመቂያይቱ ወርዶ ውሃውን በሚያናውጥበት ጊዜ፣ ቀድሞ ወደ መጠመቂያይቱ የገባ ካደረበት ማንኛውም በሽታ ይፈወስ ነበር።)

5. በዚያም ሠላሳ ስምንት ዓመት ሙሉ የታመመ አንድ ሰው ነበረ።

6. ኢየሱስ ይህን ሰው እዚያ ተኝቶ አየውና ለብዙ ጊዜ በዚህ ሁኔታ እንደ ነበር አውቆ እንዲህ አለው። "ልትድን ትፈልጋለህን?"

7. ሕመምተኛውም መልሶ እንዲህ አለው። "ጌታ ሆይ! ውሃው በሚናወጥበት ጊዜ የሚያስገባኝ ሰው የለኝም፣ እኔ ልሄድ ስል ሌላው ቀድሞኝ ይወርዳል"

8. ኢየሱስም፣ "ተነሥ! አልጋህን ተሸከምና ሂድ!" አለው።

9. ሰውዬው ወዲያው ተፈወሰ፣ አልጋውንም ተሸክሞ ሄደ። ይህም የሆነው በሰንበት ቀን ነበር።

10. ስለዚህ አይሁድ የተፈወሰውን ሰው እንዲህ አሉት። "ዛሬ ሰንበት ስለ ሆነ አልጋህን እንድትሸከም ሕግ አይፈቅድልህም!"

11. እርሱ ግን፣ "ያዳነኝ ሰው አልጋህን ተሸክመህ ሂድ!" ብሎኛል አላቸው።

12. እነርሱም፣ " 'መተኛህን ተሸክመህ ሂድ' ያለህ ሰው ማን ነው?" ብለው ጠየቁት።

13. ነገር ግን የተፈወሰው ሰው ማን እንደ ፈወሰው አላወቀም፣ ምክንያት በዚያ ስፍራ ሕዝብ ስለ ነበሩ፣ ኢየሱስ ፈቀቅ ብሎ ወደ ሕዝብ መካከል ገብቶ ስለ ነበር፣

14. ከዚህ በኋላ ኢየሱስ በቤተ ሰውየውን መቅደስ አገኘውና፣ "እነሆ፣ አሁን ድነሃል፣ ከዚህ የባሰ ነገር እንዳይደርስብህ ከእንግዲህ ወዲህ ኃጢአት አትሥራ!" አለው።

15. ሰውየውም ለአይሁድ ሄደና ራሱን ያዳነው ኢየሱስ መሆኑን ነገረ።

16. ስለዚህም አይሁድ በሰንበት ቀን ይህን ነገር ስላደረገ ኢየሱስን ያሳድዱት ጀመር።

17. ነገር ግን ኢየሱስ እንዲህ ሲል መለሰላቸው። "አባቴ እስካሁን እየሠራ ነው፣ እኔም ደግሞ እሠራለሁ"

18. እንግዲህ አይሁድ ኢየሱስን ሊገድሉት አብዝተው ይፈልጉት ነበር። ኢየሱስ ሰንበትን በመሻሩ ብቻ ሳይሆን "እግዚአብሔር አባቴ ነው" በማለት ራሱን ከእግዚአብሔር ጋር ስለ አስተካከለ ነው።

ቁ. 5-6 ኢየሱስ 38 ዓመት የሆነውን በሽተኛ "ለመዳን ትፈልጋለህ" ብሎ ጠየቀው። ብዙ ሰዎች በቤተሳይዳ በር አጠገብ አሉ። ኢየሱስ በሽተኛውን ተመለከተ። ምክንያቱም ኢየሱስ ለበሽተኛው የሚያስፈልገውን ያውቃል። ኢየሱስ ወደ እኛ መጥቶ እኛን ደካሞችን ለመፈወስ ይፈልጋል።

ቁ. 8-9 በቤተሳይዳ መጥመቂያ አጠገብ ያለው በሽተኛ ራሱን የሚያስገባ ሰውን ሲፈልግ ኢየሱስ "ተነሥ አልጋህን ተሸከምና ሂድ" አለው። ኢየሱስ በሽተኛው የሚናፍቀውን ናፍቆት ቸል ብሎ ለእርሱ የሚያስፈልገውን በቀጥታ ሰጠው። ኢየሱስ ለእኛ አንዳንድ ጊዜ የጸሎት መልስ ያለመስጠቱ ምክንያት እኛን ተስፋ እንድንቆርጥ ያደርጋል? አያደርግም። ምክንያቱም እግዚአብሔር እኛ ከምንፈልገው ምኞት አብልጦ ሊሰጥ የሚችል አምላክ ነው።

ቁ. 17 ኢየሱስ ከእግዚአብሔር ጋር ያለ ዕረፍት ይሠራል። አይሁዶች ኢየሱስ በሰንበት ሲሠራ አይተው ወቀሱት። ኢየሱስ ግን "ከእግዚአብሔር ጋር ስለሚሠራ ልጁም የእግዚአብሔርን ሥራ ተከትሎ መሥራት አለበት" አለ። ስለዚህ ኢየሱስ ያለ ዕረፍት ለእኛ ከእግዚአብሔር ጋር እንድንሠራ ፀጋውን ስለሰጠን እናመሰግናለን።

ቁ. 1-4 ብዙ ሕዝብ በቤተሳይዳ መጠመቂያ አጠገብ ተሰበሰቡ። ምክንያቱም አንዳንድ ሰዎች በቤተሳይዳ መጥመቂያ ውስጥ ገብቶ ስለሚፈወሱ ነው። ነገር ግን ሕይወትን የሚሰጠውን ኢየሱስን ያልተገናኙት አልተፈወሱም። ገና ብዙ ሕዝብ በዓለም መንገድ ችግሮችን የሚፈታ ሰው ይፈልጋሉ። እኛ ለእነርሱ ያደረግነው ነገር ምንድን ነው?

**እንጸልይ፦**   ጌታ ሆይ! የእኛን ጥልቅ ችግሮችን የፈታውን ኢየሱስን እናመሰግናለን፤ አሜን።

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

## 15. የንባብ ክፍል ዮሐንስ 5፥19-29 ወር፡ ቀን፡

## ርዕስ፦ አባትና ልጅ

19. ስለዚህ ኢየሱስ እንዲህ ሲል መለሰላቸው፣ "እኔ በእውነት እላችኋለሁ፣ አብ ሲሠራ ያየውን ከመሥራት በቀር ወልድ ከራሱ ምንም ሊሠራ አይችልም። አብ የሚያደርገውን ወልድ ደግሞ እንዲሁ ያደርጋል።

20. አብ ወልድን ስለሚወድ የሚሠራውን ሁሉ ያሳየዋል፣ እናንተም እንድትደነቁ ከዚህ የበለጠ ሥራም ያሳየዋል።

21. ምክንያቱም አብ ሙታንን እንደሚያስነሣ፣ ሕይወትንም እንደሚሰጣቸው፣ ወልድም ደግሞ እንዲሁ ለፈለገው ሁሉ ሕይወትን ይሰጣል። 22. አብ በማንም ላይ አይፈርድም፣ ነገር ግን ፍርድን ሁሉ ለወልድ ሰጥቶአል።

23. ይህንንም ያደረገው ሰዎች ሁሉ አብን እንደሚያከብሩ፣ እንዲሁም ወልድን እንዲያከብሩ ነው፣ ወልድን የማያከብር፣ የላከውን አብንም አያከብርም። 24. እኔ በእውነት እላችኋለሁ፣ ቃሌን የሚሰማ፣ በላከኝም የሚያምን የዘላለም ሕይወት አለው፣ እርሱ ከሞት ወደ ሕይወት የተሻገረ ስለ ሆነ ወደ ፍርድ አይመጣም።

25. እኔ በእውነት እላችኋለሁ፣ የሞቱ ሰዎች የእግዚብሔርን ልጅ ድምፅ የማሰሙበት ጊዜ ይመጣል፣ ጊዜውም አሁን ነው፣ የሚሰሙትም ሁሉ በሕይወት ይኖራሉ። 26. አብ በራሱ ሕይወት እንዳለው፣ እንዲሁ ደግሞ ለወልድ በራሱ ሕይወት እንዲኖረው ሰጥቶታልና። 27. አብ፣ ወልድ የሰው ልጅ ስለ ሆነም እንዲፈርድ ሥልጣን ሰጥቶታል።

28. በዚህ ነገር አትደነቁ፣ በመቃብር ውስጥ ያሉት ሁሉ የእርሱን ድምፅ የሚሰሙበት ሰዓት ይመጣል።

29. መልካም የሠሩ ለሕይወት ትንሣኤ፣ ክፉ የሠሩ ለፍርድ ትንሣኤ ይወጣሉ።

**ቁ**. 19-20 ኢየሱስ የእግዘአብሔርን ሥራ አይቶው የሚሠራና የሚፈልገውንም የሚያደርግ ነው።

ኢየሱስ ሁሉንም ሥልጣን ለእግዚአብሔር እንደሚሆን ያሳያል። እኛ የእግዚአብሔር ልጆች ሆነን ልባችን ለማድረግ በሚመኘው ሀሳብ እንኑርን?

**ቁ**. 21,24-26,29 ኢየሱስ ሙታንን የማስነሳት ሥልጣን አለው። የእግዘአብሔርንም ቃል ሰምተው የሚያምኑ ሰዎችን ከሞት ወደ ሕይወት ይመራቸዋል።

**ቁ**. 22,27-29 **ኢየሱስ ለመፍረድ ሥልጣን አለው። ኢየሱስ ስለ እኛ ኃጢአት ፋንታ የተፈረደ ሰው ነው። እግዚአብሔር ዓለምን ሁሉ እንድፈርድ ሥልጣንን ለኢየሱስ ሰጠው።** (ዳን. 7፥13-14) **እኛ ኢየሱስን የሕይወት አዳኝና ፈራጅ አድርገን አመንን**?

**ቁ**. 23 **ኢየሱስና የእግዚአብሔርን ቃል ያልተረዱት ሰዎች እግዚአብሔርን ተቃውመዋል። እኛ ሁልጊዜ የእግዚአብሔርን ቃል በመስማት እናከብራለን**? **እንጸልይ፦ ጌታ ሆይ**! **እኛ የኢየሱስ ድምፅ እንድንሰማ ስለፈቀድክና ከሞት ወደ ሕይወት ስላሸጋገርከን እናመሰግናለን፤ አሜን።**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ**? **ማን ነው**?

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ** (**በስራ ላይ ማዋል**)

7. **ፀሎት**

16. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ 5፥30-47 ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፦ ኢየሱስ ስለ ራሱ ሥራ የተናገረው ምስክርነት**

30. **እኔ በራሴ ሥልጣን ምንም ማድረግ አልችልም፤ እኔ ከአብ የሰማሁትን እፈርዳለሁ፤ የላከኝን ፈቃድ እንጂ የራሴን ፈቃድ ስለማላደርግ ፍርዴ ትክክል ነው።**

31. **እኔ ስለ ራሴ ብመሰክር፣ ምስክርነቴ እውነት አይደለም።**

32. **ነገር ግን ስለ እኔ የሚመሰክር ሌላ አለ፤ እርሱም ስለ እኔ የማመሰክረው ምስክርነት እውነት መሆኑን አውቃለሁ።**

33. **እናንተ ወደ ዮሐንስ መልክተኞች ልካችሁ ነበር፤ እርሱም ስለ እውነት መስክሮአል።**

34. **እኔ የሰው ምስክርነት የምቀበል አይደለሁም፤ ነገር ግን ይህን የምናገረው እናንተ እንድትድኑ ነው።**

35. **ዮሐንስ እንደሚነድና እንደሚበራ መብራት ነበረ፤ እናንተም ለጥቂት ጊዜ በብርሃኑ ለመደሰት ወደዳችሁ።**

36. **እኔ ከዮሐንስ ምስክርነት የበለጠ ምስክር አለኝ፤ አባቴ እንድፈጽመው የሰጠኝ ሥራ ነው፤ እኔም የምሠራው ሥራ አብ እንደ ላከኝ ይመሰክራል።**

37. **የላከኝም አብ፣ ራሱ ስለ እኔ መስክሮአል፤ እናንተ ድምፁን ከቶ አልሰማችሁም፤ መልኩንም ከቶ አላያችሁም።**

38. **አብም የላከውን ስለማታምኑ የእርሱ ቃል በእናንተ ዘንድ አይኖርም።**

39. **እናንተ በቅዱሳት መጻሕፍት የዘለዓለምን ሕይወት የምታገኙ እየመሰላችሁ፣ እነርሱን ትመረምራላችሁ፤ እነርሱም ስለ እኔ የሚመሰክሩ ናቸው።**

40. **ነገር ግን እናንተ ሕይወትን ለማግኘት ወደ እኔ መምጣት አትፈልጉም።**

41. **እኔ ከሰው ክብርን አልቀበልም፤**

42. **ነገር ግን እናንተ እግዚአብሔርን መውደድ በልባችሁ እንደሌለ አውቃችኋለሁ።**

43. **እኔ በአባቴ ስም መጣሁ፤ ነገር ግን እናንተ አልተቀበላችሁኝም፤ ነገር ግን ሌላው በራሱ ስም ቢመጣ እናንተ እርሱን ትቀበሉታላችሁ።**

44. **እናንተ እርስ በርሳችሁ ክብርን የምትፈልጉ፤ ነገር ግን ከአንዱ ከእግዚአብሔር የሚመጣውን ክብር የማትፈልጉ፣ እናንተ እንዴት እኔን ልታምኑ ትችላላችሁ?**

45. **እኔ በአባቴ ፊት የምከሳችሁ አይምሰላችሁ፤ የሚከሳችሁ አለ፤ እርሱም ተስፋ የምታደርጉበት ሙሴ ነው።**

46. እናንተ ሙሴን ብታምኑ ኖሮ፣ እኔን ባመናችሁ ነበር፣ ምክንያቱም ሙሴ የጻፈው ስለ እኔ ነው።
47. ነገር ግን እናንተ ሙሴ የጻፈውን ካላመናችሁ፣ የእኔን ቃል እንዴት ታምናላችሁ?

**ቁ.** 30 እግዚአብሔር ለኢየሱስ የመፍረድን ሥልጣን ሰጠ። ኢየሱስ የእግዚአብሔርን ፈቃደና ፍርድ ተቀብሎ ይታዘዛል። እኛ የወንጌልን ሥራ /ወንጌልን/ የሰጠውን እግዚአብሔርን እንደ ፈቃዱ ታዘዝን?

**ቁ.** 36 ኢየሱስ በሰንበት ቀን 38 ዓመት የሆነውን ሽባ ፈወሰ። ነገር ግን አይሁዶች /የአይሁድ ሰዎች/ ኢየሱስን ገሰጹት። ኢየሱስ እውነተኛ ዕረፍት የሚሰጥ እርሱ መሆኑን ገለጸ።

**ቁ.** 37-38 ኢየሱስ የእግዚአብሔርን ምስክርነት ተቀበለ። እግዚአብሔር በቃሉ በኩል ኢየሱስ ልጁ መሆኑን ገለጸ። (ማቴ. 3፥17) የአይሁድ ሰዎች እግዚአብሔርን ስላላዩና ስላልሰሙ ቃሉንም በልባቸው ስላልተቀበሉ አላመኑም።

- እኛ በየቀኑ ነቅተን እግዚአብሔር በቃሉ በኩል የሚሰጠውን በማየትና በመስማት እንቀበላለን?

**ቁ.** 39-40 ኢየሱስ የመጽሐፍትን ምስክርነት ተቀብለዋል። አይሁዶችም የዘላለም ሕይወት በመጽሐፍት ውስጥ እንዳለ አወቁ። ነገር ግን እነርሱ ኢየሱስን አላመኑም። እኛ መጽሐፍትን አይተን፦ ኢየሱስን አምነናልን?

**ቁ.** 41 ኢየሱስ ከሰዎች ክብርን አልተቀበለም። ኢየሱስ ለእግዚአብሔር ክብርን እንደ ሰጠ ይኖራል። ምክንያቱም ኢየሱስ ራሱ ከሰዎችና ከዓለም ሊከበር እንዳልመጣ አወቀ። ነገር ግን እግዚአብሔር ክብርን እንደሚሰጥ ያውቃል። ስለዚህ ሁልጊዜ ኢየሱስ እግዚአብሔር እንደ ፈቀደ ይኖራል።

**እንጸልይ፡- ጌታ ሆይ! እኛ በየቀኑ በቃሉ በኩል የኢየሱስ ምስጢር አውቀንና የኢየሱስን እውነት በመመስከር እንድንኖር እርዳን፤ አሜን!**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

17. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 6፥1–15 **ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፡– እንጀራን ከቆረሱ በኋላ**

1. **ከዚህ በኋላ ኢየሱስ ጥብርያዶስ ወደሚባለው ወደ ገሊላ ባሕር ማዶ ተሻገረ።**
2. **ብዙ ሰዎችም ኢየሱስ በሽተኞችን በመፈወስ ያደረገውን ምልክቶች ስላዩ ተከተሉት።**
3. **ኢየሱስም ወደ ተራራ ወጣና በዚያ ከደቀ መዛሙርቱ ጋር ተቀመጠ።**
4. **የአይሁድ ፋሲካ በዓል ቀርቦ ነበር።** 5. **በዚያን ጊዜ ኢየሱስ ብዙ ሕዝብ ወደ እርሱ ሲመጣ አየና ፊልጶስን፣** “**እነዚህ ሰዎች እንዲበሉ እንጀራ ከየት መግዛት እንችላለን**?” **አለው።**
6. **ኢየሱስ ይህን የተናገረው ፊልጶስን ለመፈተን ነበር እንጂ፣ ኢየሱስ ራሱ ፊልጶስን የሚያደርገውንስ ያውቅ ነበር።**
7. **ፊልጶስም እንዲህ ሲል መለሰለት።** “**ለእያንዳንዳቸው ትንሽ ትንሽ ቍራሽ እንኳ እንዲሰጣቸው የሁለት መቶ ዲናር እንጀራ አይበቃቸውም**”
8. **ከደቀ መዛሙርቱ አንዱ የስምዖን ጴጥሮስ ወንድም እንድርያስ እንዲህ አለ፣**
9. “**አምስት የገብስ እንጀራና ሁለት ዓሣ የያዘ አንድ ልጅ እዚህ አለ፣ ነገር ግን ይህ ለዚህ ሁሉ ሕዝብ ምን ይበቃል**?”
10. **ኢየሱስም፣** “**ሰዎቹ እንዲቀመጡ አድርጉአቸው**” **አለ። በዚያ ቦታ ብዙ ሣር ነበረ፣ ወንዶችም ተቀመጡ፣ ቍጥራቸውም አምስት ሺህ የሚያህል ነበር።**
11. **ኢየሱስ አምስቱን እንጀራ አንሥቶ አመሰገነ፣ ካቀረበ በኋላ ለተቀመጡት ሰዎች ዐደላቸው፣ ዓሣውንም እንዲሁ።**
12. **ሰዎችም ሁሉ በልተው ከጠገቡ በኋላ፣ ኢየሱስ ለደቀ መዛሙርቱ እንዲህ አላቸው።** “**አንድም ነገር እንዳይባክን የተረፈውንም ቍርስራሽ ሰብስቡ**”
13. **ስለዚህ ደቀ መዛሙርቱ ከተበላው አምስት የገብስ እንጀራ የተረፈውን ቍርስራሽ ሰብስበው አሥራ ሁለት መሶብ ሞሉ።**
14. **ሰዎቹም ኢየሱስ ያደረገውን ተአምር ባዩ ጊዜ እንዲህ አሉ።** “**በእርግጥ ይህ ወደ ዓለም የሚመጣው ነቢይ ነው**!”
15. **ኢየሱስም ሰዎቹ መጥተው በግድ ሊያነግሡት እንዳሰቡ አውቆ እንደገና ብቻውን ወደ ተራራ ሄደ።**

ቁ. 5,11 ኢየሱስ ለተከተሉት ሰዎች ችግራቸውን ረዳቸው። እንደዚሁም ኢየሱስ እርሱን ለሚፈልጉ ሰዎች ሁልጊዜ ችግራቸውን ይቀበላል።

ቁ. 10-13 ኢየሱስ በአምስት እንጀራና በሁለት ዓሣ አምስት ሺህ ሰዎችን መገባቸው።ሁሉም ከበሉ በኋላ አስራ ሁለት ቅርጫት ቀረ። ኢየሱስ ለክርስቲያኖች የሕይወት እንጀራን ሰጥቶ አሳያቸው። ደግሞም ለአማኞቹ የሚያስፈልጋቸውን በሙሉ ይሰጣቸዋል።

ቁ. 14,15 ሰዎች ይህን ተአምራት አይተው ኢየሱስን እንደ ንጉሥ ማድረጋቸውን አውቆ ከለከላቸው። እኛ የምንፈልገው ምን ዓይነት ንጉሥ ወደ ሕይወታችን መጥቶ እንዲቆጣጠር ነው?

ቁ. 5,6 ዛሬ እኛም እንደ ኢየሱስ ዓይኖቻችን ተከፍቶ ለሰዎች የሚያስፈልገውን አይተን ለመርዳት እንሥራ!

ቁ 7-9 ፊልጵስና እንድሪያስ ባዶ ሜዳውን ወደ አዳራሽ የለወጠውን የኢየሱስን ሥልጣን አላዩም። ምክንያቱም እነርሱ በዓይናቸው ፊት አሁን የሚሆነውን ያያሉ። ለእነርሱ በማይቻል ሁኔታ በሀሳባቸውም ማመን የማይችሉ ሁሉን ነገሮችን የቻለውን ኢየሱስ ሥልጣን አዩ።

እንጸልይ፦ ጌታ ሆይ! ለረኀብተኛ ሕይወታችን የሕይወት እንጀራን ስለሰጠህና ስለእግዚአብሔር ፀጋህ እናመሰግናለን፤ አሜን።

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

## 18. የንባብ ክፍል ዮሐንስ 6፥16–29 ወር፡ ቀን፡

## ርዕስ፡– እኔ ነኝና አትፍሩ!

16. በመሸም ጊዜ ደቀ መዛሙርቱ ወደ ባሕር ወረዱ፣

17. ደቀ መዛሙርቱም በጀልባ ተሳፍረው በባሕር ማዶ ወደ ቅፍርናሆም ሄዱ፤ በዚያን ሰዓት ጊዜው ጨልሞ ነበር፣ ኢየሱስም ገና ወደ እነርሱ አልመጣም ነበር።

18. በዚያን ጊዜ ኀይለኛ ንፋስ ይነፍስ ስለ ነበር፣ ባሕሩ ተናወጠ።

19. ደቀ መዛሙርቱ አምስት ወይመ ስድስት ኪሎ ሜትር ያህል እንደ ቀዘፉ፣ ኢየሱስ በውሃ ላይ እየተራመደ ወደ ጀልባዋ ሲቀርብ አይተው ፈሩ።

20. እርሱ ግን "እኔ ነኝ! አትፍሩ!" አላቸው።

21. ደቀ መዛሙርቱም በደስታ ኢየሱስን ወደ ጀልባዋ ተቀበሉት፣ ወዲያውኑ ጀልባዋ ወደሚሄዱበት ቦታ ደረሰች።

22. በማግሥቱ በባሕሩ ማዶ የቀሩት ሰዎች በዚያ አንዲት ጀልባ ብቻ እንደ ነበረ፣ ኢየሱስ እንዳልገባና ደቀ መዛሙርቱ ብቻቸውን እንደ ሄዱም አወቁ።

23. ከዚያም በኋላ፣ ሌሎች ጀልባዎች ከጥብርያዶስ መጡ፣ ይህ ኢየሱስ የምስጋና ጸሎት ወደ አደረገበትና ሕዝቡ እንጀራ ወደ በላበት ስፍራ አጠገብ ነው።

24. ሰዎቹም ኢየሱስ ወይም ደቀ መዛሙርቱ በእዚያ እንደሌሉ ባዩ ጊዜ በነዚያ ጀልባዎች ገብተው ኢየሱስን ፍለጋ ወደ ቅፍርናሆም ሄዱ።

25. ሰዎቹም ከባሕሩ ማዶ ባገኙትም ጊዜ፣ "መምህር ሆይ፣ መቼ ወደዚህ መጣህ?" አሉት።

26. ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰላቸው፣ "እኔ በእውነት እላችኋለሁ፣ እናንተ የምትፈልጉኝ እንጀራ ስለ በላችሁና ስለ ጠገባችሁ ነው እንጂ ተአምራት ስላያችሁ አይደለም።

27. ለሚጠፋ እንጀራ አትሥሩ፣ ነገር ግን የዘለዓለም ሕይወት ለሚሆነው ምግብ ሥሩ። የሰው ልጅ ይህ ምግብን ለሚሰጣችሁ፣ እግዚአብሔር አብ ማረጋገጫ ማኅተሙን በኢየሱስ ላይ አትሞአልና።

28. እንግዲህ ሰዎቹ እንዲህ አሉት። "ታዲያ፣ እኛ የእግዚአብሔርን ሥራ ለመሥራት ምን ማድረግ ይገባናል?"

29. ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰላቸው። "የእግዚብሔር ሥራማ እግዚአብሔር በላከው ማመን ነው"

**ቁ**. 16−19 ኢየሱስ በዓውሎ ነፋስና በከፍተኛ ማዕበል መካከል በባህር ላይ እየተራመደ ወደ ደቀ መዛሙርቱ መጣ። ይህ ኢየሱሰ የውሃውን ኃይል ተቆጣጥሮ በውሃ ላይ ተራምዶ በመሄድ እርሱና እግዚአብሔር እኩል መሆኑን ገለጸ። (ኢዮብ 9፡8) ወደ ሕይወታችን ጨለማና ከፍተኛ ማዕበል በሚመጣበት ጊዜ ኢየሱስን መመልከትን ትተን እንፈራለን? በከፍተኛ ማዕበሉ ውስጥ እየተራመደ የመጣውን ኢየሱስን ዓይኖቻችን ተከፍቶ ማየት ያስፈልጋል።

**ቁ**. 20,21 ኢየሱስ "እኔ ነኝና አትፍሩ" አላቸው። ይህ ማለት ኢየሱስ ብቻ ለሕይወታችን እውነተኛ ዕረፍትን የሚሰጥ መሚሕ መሆኑን ይገልጻል። በችግርም ውስጥ ላለቸው ደቀ መዛሙርት "እኔ ነኝና አትፍሩ!" ብሎ አጽናናቸው። ደቀ መዛሙርቱም የጌታን ድምፅ በእምነት ሰምተው ኢየሱስን ወደ ራሳቸው ጀልባ ተቀበሉት። ኢየሱስን ለሚቀበሉ ሰዎች የሚሆዱበት የተሰፋ ወደብ ይሆናል። (መዝ. 107፡28−30)

- እኛ ከጌታ ጋር የምንሄድበትን ጉዞ እየተጠባበቅን እንሄዳለን።

**ቁ**. 25−27 ኢየሱስ በተሳሳተ ምኞት የራሱን ተአምራት ለሚፈልጉ ሰዎች እይታቸውን ለወጠ። ኢየሱስ ሰዎችን ወደ ትክክለኛ መንገድና ተድላን እንዲያዩ ይፈልጋል። ዛሬ በእግዚአብሔር ቃል በኩል ስህተታችንን ማረም እንድንችል እንጸልያለን።

**ቁ**. 22−24,26 አንዳንዶች በብዙ ጀልባ ኢየሱስን ይፈልጋሉ። ነገር ግን እነርሱ የሚፈልጉት ኢየሱስን ሳይሆን ኢየሱስ የሠራውን ድንቅ ተአምራትን ነው። እኛ ኢየሱስን የምንከተልበት ስለምኞታችን ነው? ወይስ መንፈሳዊ ሕይወታችን አብልጠን ነው?

**እንጸልይ፦ ጌታ ሆይ! እኛ በዓለም የሚቀረውን ዕቃዎችንና ገንዘብን ሳንፈልግ ሁልጊዜ ኢየሱስ እንደሚፈልገው መኖር እንድንችል እርዳን፤ አሜን!**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

## 19. የንባብ ክፍል ዮሐንስ 6፥30–40 ወር፡ ቀን፡

## ርዕስ፡– ኢየሱስ የሕይወት እንጀራ ነው።

30. እነርሱም እንዲህ ብለው ጠየቁት፣ "እኛ አይተን በአንተ እንድናምንህ ምን ተአምር ታደርጋለህ? ምንስ ትሠራለህ?

31. 'እንዲበሉ ከሰማይ እንጀራን ሰጣቸው' ተብሎ እንደ ተጻፈ፣ አባቶቻችን በምድረ በዳ መና በሉ።"

32. ኢየሱስም እንዲህ አላቸው፣ "እኔ በእውነት እላችኋለሁ፣ እናንተ ከሰማይ የወረደውን እንጀራ የሰጣችሁ ሙሴ አይደለም፣ ከሰማይ እውነተኛውን እንጀራ የሚሰጣችሁ አባቴ ነው፣

33. የእግዚአብሔር እንጀራ ከሰማይ የሚወርድና ለዓለም ሕይወትን የሚሰጥ ነው።"

34. ስለዚህ ሰዎቹ፣ "ጌታ ሆይ! ይህን እንጀራ ሁልጊዜ ስጠን!" አሉት።

35. ኢየሱስም እነዲህ አላቸው፣ "እኔ የሕይወት እንጀራ ነኝ፣ ወደ እኔ የሚመጣ ከቶ አይራብም፣ በእኔም የሚያምን ከቶ አይጠማም።

36. ነገር ግን እኔ እንደ ነገርኋችሁ፣ እናንተ አይታችሁኝም እንኳ አታምኑም።

37. አብ የሚሰጠኝ ሁሉ ወደ እኔ ይመጣል፣ ወደ እኔ የሚመጣውንም ከቶ ወደ ውጭ አላወጣውም፣

38. እኔ ከሰማይ የወረድሁት የራሴን ፈቃድ ለማድረግ አይደለም፣ የላከኝን የእግዚአብሔርን ፈቃድ ለመፈጸም ነውና፣

39. የላከኝ ፈቃድ፣ ከሰጠኝ ሁሉ አንድ እንኳ ሳይጠፋብኝ በመጨረሻው ቀን እንዳስነሣቸው ነው።

40. የአባቴ ፈቃድ ወልድን አይቶ በእርሱ የሚያምን ሁሉ የዘላለም ሕይወት እንዲኖረው ነው፣ እኔም በመጨረሻው ቀን አስነሣዋለሁ።"

**ቁ.** 32, 33, 35 ኢየሱስ ለዓለም ሕይወትን የሚሰጥ የእግዚአብሔር እንጀራ ነው። ይህ እንጀራ እስራኤላዊያን በምድረ በዳ በሙሴ በኩል ከበሉት መና በመሠረታዊ ሀሳቡ ይለያል። ይህ መና ለእኛ እንደገና የዘላለም ሕይወት የሚሰጥ አይደለም። በሙሴ በኩል የተሰጣቸውን መና የበሉት እንደገና ይራባሉ ይጠማሉም። ነገር ግን ኢየሱስ ከሰማይ የመጣው ወደ ራሱ ለሚመጡ ሰዎች የሕይወትን እንጀራ ይሰጣቸዋል። ስለዚህ

አሁን የዓለም መናን የሚፈልገውን ሕይወታችን ለወጠን የሰማዩን ምግብ እየፈለግን ሊንኖር ያስፈልጋል።

ቁ. 37 ኢየሱስ ወደ ራሱ የመጡትን ወደ ውጪ አያባርረውም። እኛ ወደ ኢየሱስ ሄደናል? እኛ ወደ ኢየሱስ ካልሄደን አሁን ሄደን የዘላለምን ሕይወት ወራሾች እንሁን! የእኛን ድነት ሊያናውጥ ያለው ነገር ምንድን ነው? በዓለም ላይ እኛን ከኢየሱስ ሊለየን የሚችል ምንም እንደሌላ አስታውሱ።

ቁ. 38-40 ኢየሱስ የእግዚአብሔርን ፈቃድ ለማድረግ እስከ መስቀል ሞት ድረሰ ታዘዘ። (ፊልጵ. 2፥8) የእግዚአበሔር ፈቃድ ሰዎች ሁሉ ኢየሱስን አምኖ ድነትን እንድቀበሉ ነው። ደግሞም በመጨረሻ ቀን የትንሣኤ ዕድል እንዲያገኙም ይፈልጋል። ኢየሱስ ስለ እግዘአብሔር ፈቃድ ኖረ። እግዘአብሔር በሕይወታችን ፈቃዱን ሊያደርግ ይፈልጋል።

ቁ. 30, 31 ደቀ መዛሙርቱ ከሙሴ ተአምራት ይልቅ የኢየሱስ ተአምራት በልጦ እንዲገኝ ይፈልጋሉ። ምክንያቱም ኢየሱስ ከሙሴ ተአምራት የሚበልጥ እንደሚያደርግ አሰበዋልና። የእምነት ዓይኖች ሳይከፈት ኢየሱስን ማወቅ አይቻልም። በመጀመሪያ መንፈሳዊ ዓይኖቻችን እንዲከፈት እንፀልያለን።

እንጸልይ፦ ጌታ ሆይ! ሁልጊዜ የእኛ መንፈሳዊ ዓይኖቻችን ተከፍቶ ኢየሱስን አምነን በሕይወት እንድንኖር እርዳን፤ አሜን!

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

20. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ 6፥41-59 ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፡- ይህን እንጀራ የሚበላ የዘላለም ሕይወት አለው።**

41. ስለዚህ አይሁድም፣ "ከሰማይ የወረደ እንጀራ እኔ ነኝ" በማለቱ አይሁድ በኢየሱስ ላይ አጕረመረሙ፣

42. እነርሱም እንዲህ አሉ፣ "ይህ የዮሴፍ ልጅ ኢየሱስ አይደለምን? ታዲያ፣ አሁን እርሱ እንዴት 'ከሰማይ ወረድኩ' ይላል?"

43. ኢየሱስም መልሶ እንዲህ አላቸው፣ "እርስ በርሳችሁ አታጕረምርሙ፣

44. የላከኝ አብ ካልሳበው በቀር ማንም ወደ እኔ መምጣት አይችልም፣ ወደ እኔ የሚመጣውንም በመጨረሻ ቀን አስነሣዋለሁ።

45. በነቢያት መጻሕፍት፣ 'ሰዎች ሁሉ ከእግዚአብሔር የተማሩ ይሆናሉ' ተብሎ ተጽፎአል፣ ስለዚህ ከአብ ሰምቶ የተማረ ሁሉ ወደ እኔ ይመጣል።

46. ይህም ማለተ አብን ያየው ሰው አለ ማለት አይደለም፣ አብን ያየ ማንም የለም፣ ከእግዚአብሔር ዘንድ የመጣው እርሱ ብቻ አብን አይቶአል።

47. እኔ በእውነት እላችኋለሁ፣ (በእኔ) የሚያምን ሰው የዘለዓለም ሕይወት አለው።

48. እኔ የሕይወት እንጀራ ነኝ።

49. አባቶቻችሁ በምድረ በዳ መና በሉ፣ ነገር ግን እነርሱ ሁሉ ሞቱ፣

50. ነገር ግን ይህ ከሰማይ የወረደው እንጀራ ነው፣ ማንም ይህን እንጀራ የሚበላ በፍጹም አይሞትም።

51. እኔ ከሰማይ የወረደ ሕያው እንጀራ ነኝ፣ ማንም ከዚህ እንጀራ ቢበላ ለዘላለም ይኖራል፣ ይህም እንጀራ፣ ለዓለም ሕይወት እንዲሆን የምሰጠው ሥጋዬ ነው።"

52. እንግዲህ አይሁድ፣ "ይህ ሰው ሥጋውን እንድንበላ እንዴት ሊሰጠን ይችላል?" በማለት እርስ በርሳቸው ይከራከሩ ጀመር።

53. ስለዚህ ኢየሱስም እንዲህ አላቸው፣ "እኔ በእውነት እላችኋለሁ፣ እናንተ የሰውን ልጅ ሥጋውን ካልበላችሁና ደሙንም ካልጠጣችሁ በራሳችሁ ሕይወት የላችሁም።

54. ማንም ሥጋዬን የሚበላና ደሜንም የሚጠጣ የዘላለም ሕይወት አለው፣ እኔም በመጨረሻው ቀን አስነሣዋለሁ፣

55. ምክንያትም ሥጋዬ እውነተኛ ምግብ፣ ደሜም እውነተኛ መጠጥ ነውና፣

56. ማንም ሥጋዬን የሚበላና ደሜን የሚጠጣ ሁሉ በእኔ ይኖራል፣ እኔም በእርሱ እኖራለሁ።

57. ሕያው አብ እንደ ላከኝ፣ እኔም ከእርሱ የተነሣ በሕይወት እንደምኖር፣ እንዲሁም የሚበላኝ ከእኔ የተነሣ ሕያው ይሆናል።
58. ይህ ከሰማይ የወረደ እንጀራ ነው፣ አባቶቻችሁ መና በሉ፣ ሞቱም፣ ነገር ግን ይህን እንጀራ የሚበላ ለዘላለም ይኖራል።" 59. ኢየሱስ ይህን የተናገረው በቅፍርናሆም በምኵራብ በሚያስተምርበት ጊዜ ነበር።

**ቁ**. 44, 46 ኢየሱስ ወደ ራሱ ለሚመጡት የሕይወት ትንሣኤ ይሰጣል። እኛ ኢየሱስን አምነን መዳንን እንድንቀበል የእግዚአብሔር ሙሉ ሥልጣን ነው። ቃሉን ካልተረዳን እግዚአብሔር የሚመራውን አይሰጥም። ደግሞም ከኢየሱስ ጋር የግል ግንኙነት አይኖረንም። ስለዚህ ዛሬ እኛ ቃሉን አንብበን እንደቃሉ እንድንኖር እግዚአብሔር እኛ ወደ ኢየሱስ እንድንመጣ ይናገራል።

**ቁ**. 47−51,58 ኢየሱስ ለእኛ የዘላለም ሕይወት የሚሰጥ እንጀራ ነው። በምድረ በዳ የእስራኤል ሕዝብ መናን የበሉ ሁሉ ሞቱ። ነገር ግን ይህ የሕይወት እንጀራን ወይም ኢየሱስን የሚበሉት አይሞቱም ለዘላለም ይኖራሉ። ምክንያቱም ኢየሱስ ለእኛ የሰጠው ድኅነት ከዓለም አይደለምና። ነገር ግን ከሰማይ የመጣ መንፈሳዊ ሕይወትን የሚሰጥ ነው።

**ቁ**. 53−58 ኢየሱስ ለእኛ የዘላለም ሕይወት የሰጠው በመስቀል ላይ ሞቶ ነው። እኛ የኢየሱስ ሥጋና ደም መብላትና መጠጣት አለብን። "የኢየሱስ ሥጋንና ደምን መብላትና መጠጣት" ማለት በመስቀል ላይ ተሰቅሎ የሞተውን ኢየሱስን ፈጽመን በልባችን አጥብቀን መቀበል ማለት ነው። /ማቴ. 26፥26−28/

**ቁ**. 41, 42, 52 አይሁዶች ኢየሱስ በሥጋ መምጣቱን ስለትህትናው በቀላል አይተው መሲሕ መሆኑን አልተቀበሉም። ለእነዚህ ኢየሱስን በሥጋ ብቻ ላዩት አይሁዶች እውነተኛ በር አልተከፈተላቸውም። እነርሱ በምድረ በዳ መናን የበሉ

**የእስራኤል ሕዝብ በማጉረምረም አድርገው ጠፍተዋል። ዛሬም የእኛ ማጉረምረም የእግዚአብሔርን ፀጋ ማሰናከያ የሚያስታውስ ነው።**

**እንጸልይ፦ ጌታ ሆይ! ዛሬ የሕይወትን እንጀራ በሚሰጠው በኢየሱስ ውስጥ እንድንኖር እርዳን፤ አሜን!**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

## 21. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 6፥60−71 **ወር፡ ቀን፡**

## **ርዕስ፡− የሕይወትን ግብዣ እንቢ ብለው የወጡት ሰዎች።**

60. **ከደቀ መዛሙርቱ ብዙዎች ይህን ሲሰሙ፣ "ይህ የሚያስጨንቅ ቃል ነው፣ ማን ሊቀበለው ይችላል?" አሉ።**

61. **ኢየሱስም ደቀ መዛሙርቱ ስለዚህ ነገር እንዳጒረመረሙ በገዛ ራሱ አውቆ እንዲህ አላቸው፣ "ይህ ነገር ያሰናክላችኋልን?** 62. **እንግዲህ የሰው ልጅ ቀድሞ ወደ ነበረበት ሲወጣ ብታዩ ምን ልትሉ ነው?**

63. **ሕይወትን የሚሰጥ የእግዚአብሔር መንፈስ ነው፣ ሥጋ ግን ምንም አይጠቅምም። እኔ ለእናንተ የተናገርኩት ቃል መንፈስ ነው፣ ሕይወትም ነው፣** 64. **ነገር ግን ከእናንተ መካከል የማያምኑ አንዳንዶች አሉ።" ይህም፣ ኢየሱስ እነማን እንዳላመኑና ማን ራሱን አሳልፎ እንደሚሰጠው ቀድሞውኑ ያውቅ ስለ ነበር ነው።**

65. **ኢየሱስ፣ 'ስለዚህ እንዲህ አልኋችሁ፣ "ከአብ የተፈቀደለተ ካልሆነ በቀር ወደ እኔ መምጣት የሚችል የለም" ' አለ።** 66. **በዚህም ምክንያት ከደቀ መዛሙርቱ ብዙዎቹ ወደ ኋላ ተመለሱ፣ ከዚያን ጊዜ ጀምሮም ኢየሱስን አልተከተሉትም።** 67. **ስለዚህ ኢየሱም አሥራ ሁለቱን፣ "እናንተም ደግሞ መሄድ ትፈልጋላችሁ?" አላቸው።**

68. **ስምዖን ጴጥሮስም እንዲህ ሲል መለሰለት፣ "ጌታ ሆይ፣ ወደ ማን እንሄዳለን? አንተ የዘላለም ሕይወት ቃል አለህ፣**

69. **እኛስ አንተ የእግዚአብሔር ቅዱስ እንደ ሆንህ አምነናል፣ አውቀናልም።"** 70. **ኢየሱስም መልሶ፣ "እኔ እናንተን አሥራ ሁለታችሁን የመረጥኋችሁ አይደለሁምን? ነገር ግን ከእናንተ አንዱ ዲያብሎስ ነው" አላቸው።**

71. **ይህንንም ያለው ስለ ስምዖን ልጅ ስለ አስቆሮታዊው ይሁዳ ነበር፣ ይሁዳ ከአሥራ ሁለቱ አንዱ ቢሆን ኢየሱስን ኋላ አሳልፎ የሚሰጥ እርሱ ስለ ነበር ነው።**

**ቁ**. 61−63 **ኢየሱስ ለደቀ መዛሙርቱ ስለ ሥጋውና ስለ ደሙ በቀላሉ ገለጸ። ይህ ኢየሱስ ለእኛ ሕይወትን ሰጥቶ በመስቀል ላይ እንደሚሞት ከመንፈስ ቅዱስ ተረዳ። ስለዚህ ሁልጊዜ እኛ የእግዚአብሔርን ቃል ስናነብ ዓይናችን ከፍቶልን እንድናስተውል እንጸልያለን።(መዝ.ዳዊ.** 119፥18)

**ቁ**.67−69 **ኢየሱስ ብዙ ሰዎች ከወጡ በኋላ ለደቀ መዛሙርቱ እንዲህ ሲል ተናገረ። "እናንተም ልትሄዱ ትፈልጋላችሁን?" እኛንም ደግሞ እንደዚህ ብሎ ይጠይቀናል።**

“እናንተም ልትሄዱ ትፈልጋላችሁን?” እኛ ከጌታ ጋር በሕይወት መስቀሉን ይዘን እርሱን እንከተላለን።

**ቁ.** 60 የኢየሱስን ቃል መስማት የከበደባቸው ሰዎች የራሳቸውን ምኞት ያለመጣላቸውና ያለመስተካከላቸው ምክንያት ነው። ይህም የእኛ የልብ ችግር ነው። እኛ የእግዚአብሔርን ቃል ስናነብ በሥጋ ዓይን ብንመለከት ቃሉን አናስተውልም። ነገር ግን የዘላለም ሕይወትን ብናይ እናስተውላለን። ለእኛ የእግዚአብሔር ቃል እንዴት ይሰማናል?

**ቁ.** 66 የእግዚአብሔርን ቃል ሳያስተውሉ ኢየሱስን በሥጋ ምኞት የሚወስዱ የሥጋ ምኞታቸውን ከተቀበሉ በኋላ በመጨረሻ ጌታን ይተዋሉ። እኛ ስለ ምን ኢየሱስን እንከተላለን?

**እንጸልይ፡- ጌታ ሆይ፤ እኛ የሕይወትን ቃል የሚሰጥ ኢየሱስን ከቶ እንዳንተው እርዳን። አሜን!**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

## 22. የንባብ ክፍል ዮሐንስ 7፥1−13 ወር፡ ቀን፡

### ርዕስ፡− የእግዚአብሔር ጊዜ።

1. ከዚህ በኋላ ኢየሱስ በገሊላ ይዘዋወር ነበር፣ አይሁድ ሊገድሉት ይፈልጉ ፈለጉ፣ በይሁዳ አውራጃ ሊዘዋወር አልፈለገም፣ 2. በዚያን ጊዜ የአይሁድ የዳስ በዓል ቀርቦ ነበር።

3. እንግዲህ የኢየሱስ ወንድሞች ወደ ኢየሱስ ቀርበው እንዲህ አሉት፣ "ደቀ መዛሙርትህ የምታደርገውን ሥራ እንዲያዩ፣ ከዚህ ተነሥተህ ወደ ይሁዳ ምድር ሂድ፣ 4. በግልጥ ለመታወቅ የሚፈልግ ሰው ሥራውን በስውር አያደርግም፣ አንተም እነዚህን ነገሮች የምታደርግ ከሆነ፣ ራስህን ለዓለም ግለጥ።"

5. ይህንንም ያሉበት ምክንያት ወንድሞቹ እንኳ በኢየሱስ ስላላመኑ ነው።

6. ኢየሱስም እንዲህ አላቸው፣ "የእኔ ጊዜ ገና አልደረሰም፣ ነገር ግን የእናንተ ጊዜ ሁልጊዜ የተመቸ ነው።

7. ዓለም እናንተን ሊጠላ አይችልም፣ ነገር ግን እኔን ይጠላኛል፣ ይህ እኔ ለዓለም ሥራ ክፉ መሆኑን ስለምመሰክርበት ነው። 8. እናንተ ወደ በዓሉ ሂዱ፣ እኔ ጊዜዬ ገና ስላልደረሰ ወደዚህ በዓል አልሄድም።"

9. ይህንንም ብሎ ኢየሱስ በገሊላ ቀረ።

10. ነገር ግን ወንድሞቹ ወደ በዓሉ ከሄዱ በኋላ ኢየሱስ በግልጥ ሳይሆን በስውር ወደ በዓሉ ሄደ።

11. በበዓሉም ላይ አይሁድ፣ "እርሱ የት አለ?" እያሉ ይፈልጉት ነበር።

12. በሕዝብም መካከል ስለ ኢየሱስ በሹክሹክታ ይነጋገሩ ነበር፣ አንዳንዶቹ፣ "እርሱ ደግ ሰው ነው" ሲሉ፣ ሌሎች ደግሞ፣ "አይደለም፣ እርሱ ሕዝቡን ያስታል" ሥሉ ነበር።

13. ነገር ግን ሕዝብ አይሁድን ከመፍራት የተነሣ ስለ ኢየሱስ በግልጽ የተናገረ አልተናገረም።

**ቁ.** 6−9 ኢየሱስ በዓለም ላይ የሚፈልገው ዓለምን ለመቆጣጠር አይደለም። ነገር ግን እንደ እግዚአብሔር ፈቃድ ሁሉንም አደረገ። እኛ ደግሞ የጌታ ጊዜ በጣም ጥሩ ጊዜ መሆኑን አውቀን ጌታ የሚሠራውን ጊዜ አምነን እንቆያለን።

**ቁ**. 10 ኢየሱስ ወደ ኢየሩሳሌም "በሥውር" ሄደና "በደስታ" መጮኸቸውን አውቆ ዝም አለ። (ዮሐ.12፥12-15) ይህ ወደ ኢየሩሳሌም መሄዱ ሰዎች እንዲፈልጉ ራሱን ለዓለም ላለማሳወቅ ፈልጐ ነው። ምክንያቱም የእግዚአብሔርን ፈቃድ ስለሚያደርግ ነው።

**ቁ**. 2-5 የኢየሱስ ወንድሞች ኢየሱስን አናገሩት። ከኢየሩሳሌም የዳስ በዓል ምቹ ጊዜን እንዲጠቀም ራሱንም ለዓለም እንዲገልጽ ለመኑት። ነገር ግን ይህ ኢየሱስን የማያምኑና የኢየሱስን ቃል የማያስተውሉ የሰዎች አስተሳሰብ ነው። እኛ ደግሞ እንደ ኢየሱስ ወንድሞች ከሰዎች እንደዛው ይልቅ እውቅና ለመቀበል አላደረግንምን? ወይንም የእግዚአብሔር የፈቃዱን እውነቅት ለማድረግ ፈለግን?

**ቁ**. 6 የኢየሱስ ወንድሞቹ ከዓለም ጋር ያለውን ጥላቻን አልተቀበሉም። ምክንያቱም እነርሱ ኢየሱስን ስለማያምኑ ነው። እኛ ለኢየሱስ ወይም ለዓለም ለየትኛው ቅርብ ነን?

**እንጸልይ፡-** ጌታ ሆይ፤ እኛ በችግራችን ውስጥ ብንሆንም የእግዚአብሔርን ጊዜ በእምነት እንድንጠብቅ እርዳን። አሜን!

1. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ

2. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት

3. እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?

4. የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና

5. ትምህርት

6. ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)

7. ፀሎት

## 23. የንባብ ክፍል ዮሐንስ 7፣14–24 ወር፡ ቀን፡

## ርዕስ፡– ስለ ኢየሱስ አለመግባባት

14. በበዓሉም አጋማሽ ላይ ኢየሱስ ወደ ቤተ መቅደስ ሄዶ ያስተምር ጀመር። 15. አይሁድም በመደነቅ እንዲህ አሉ። "ይህ ሰው ሳይማር መጻሕፍትን እንዴት ሊያውቅ ቻለ?"

16. ኢየሱስም መልሶ እንዲህ አላቸው፤ "የእኔ ትምህርት ከራሴ ሳይሆን፣ ከላከኝ የመጣ ነው።

17. ማንም የእግዚአብሔርን ፈቃድ ለማድረግ ቢፈልግ፣ የእኔ ትምህርት ከእግዚአብሔር ወይም ከራሴ የመጣ መሆኑን ለይቶ ያውቃል፤ 18. ከገዛ ራሱ የሚናገር የገዛ ራሱን ክብር ይፈልጋል፤ ነገር ግን የላከውን ክብር የሚፈልግ እርሱ እውነተኛ ነው፤ ሐሰትም የለበትም። 19. ሙሴ ሕግን አልሰጣችሁምን? ነገር ግን ከእናንተ ሕግን የሚፈጽም ማንም የለም። እናንተ ለምን ልትገድሉኝ ትፈልጋላችሁ?" 20. ሕዝቡም መለሱ እንዲህ አሉት። "አንተ ጋኔን አለብህ፤ ማን አንተን ሊገድል ይፈልጋል?"

21. ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰላቸው፤ "እኔ አንድ ሥራ ሠራሁ፤ እናንተም ሁላችሁ ትደንቃላችሁ።

22. ሙሴ የግዝረትን ሥርዓት ሰጣችሁ፤ ይህም ሥርዓት ከሙሴ አይደለም፣ ከአባቶች መጣው እንጂ፤ ስለዚህ እናንተም በሰንበት ሰውን ትገርዛላችሁ። 23. እንግዲህ የሙሴ ሕግ እንዳይሻር ሰው በሰንበት መገረዝን የሚቀበል ከሆነ፣ እኔ በሰንበት ቀን የሰውን ሁለንተና በመፈወሴ ስለምን ትቈጣላችሁ?

24. እናንተ ብቻ የሰው መልክ አይታችሁ አትፍረዱ፤ ትክክለኛው ፍርድ ፍረዱ።"

ቁ. 16,18 የኢየሱስ ትምህርት ከእግዚአብሔር እውቀት የመጣ ነው። ኢየሱስ ከራሱ ወይም ከሌሎች ምንም ትምህርት አላመጣም። ብቻ ኢየሱስ ከላከው ከእግዚአብሔር ቃልን ተቀብሎ አስተማረ። ለእግዚአብሔርም ክብር ጸለየ። እኛ ስናስተምርና ቃሉን ስንናገር ማን ነው ክብርን የሚቀበለው?

ቁ. 21–23 ኢየሱስ በሰንበት ቀን ሽባውን በመፈወስ የእግዚአብሔርን ክብር ገለጸ። አይሁድ የሰንበትን ሥርዓት የሃይማኖታቸው አድርገው ይጠብቃሉ። ነገር ግን

ኢየሱስ የሰንበትን እውነተኛ ትርጉም ገለጸ። አምልኮአችንን የሚቀበለውን የእግዚአብሔርን ፈቃድ መፈጸም እውነተኛ አምልኮ ነው።

**ቁ.** 17,18 የእግዚአብሔርን ፈቃድ ለሚያደርጉ ሰዎች የእግዚአብሔር ራዕይ ወይም መገለጥ ተዘጋጅቶ ይኖራል። መንፈሳዊ እውነት ከአንዳች ከልዩ ትምህርትና ከትዕዛዝ በኩል አይመጣም። ነገር ግን ትሁት በሆነው በእግዚአብሔር ቃል ፊት የራሱን አሳብ በሙሉ በማስቀመጥ ሲታዘዝ የእግዚአብሔርን ፈቃድ ይረዳል። እኛ የእግዚአብሔርን ቃል ስናነብ ብቻ እግዚአብሔርን በማክበርና በመታዘዝ ልብ እናነባለንን?

**ቁ.** 19,20 አይሁዶች ኢየሱስን ለመግደል ፈለጉ። ነገር ግን ሕግን እንዳልጠበቁ ኢየሱስ ገለጸ። እኛ በየቀኑ የእግዚአብሔርን ቃል እየወደድን በምላሳችን ብቻ እንናገራለን። ነገር ግን ሕይወታችን በቃሉ መኖሩን አለመግለጹ እኛ እንደ አይሁዶች ሰዎች መሆናችንን ነው።

**እንጸልይ፦** ጌታ ሆይ፤ እኛ ሁልጊዜ የእግዚአብሔርን ቃል በመታዘዝ ለጌታ ክብርን እንድንሰጥ እርዳን። አሜን!

1. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ

2. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት

3. እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?

4. የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና

5. ትምህርት

6. ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)

7. ፀሎት

24. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 7፥25-36 **ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፡- ኢየሱስ ከእግዚአብሔር ዘንድ የመጣ ሰው ነው**

25. **በዚህ ጊዜ ከኢየሩሳሌም ሰዎች አንዳንዶቹ እንዲህ አሉ፣ "ይህ ሰው ሰዎች ሊገድሉት የሚፈልጉት እርሱ አይደለምን**?

26. **እነሆ፣ እርሱ በግልጥ ይናገራል፤ እነርሱም ምንም ቃል አይናገሩትም፤ አለቆቹ ይህ ሰው በእውነት ክርስቶስ መሆኑን አውቀው ይሆን**?

27. **ነገር ግን ይህ ሰው ከወዴት እንደ ሆነ እኛ እናውቃለን፤ ክርስቶስ ሲመጣ ከወዴት እንደ ሆነ ማንም አያውቅም።"**

28. **ኢየሱስ በቤተ መቅደስ ሲያስተምር ድምፁን ከፍ አድርጎ እንዲህ አለ፣ "እናንተ እኔን ታውቁኛላችሁ፣ ከወዴትም እንደ መጣሁ ታውቃላችሁ፣ ነገር ግን እኔ በራሴ ሥልጣን አልመጣሁም፤ የላከኝ እርሱ እውነተኛ ነው፤ እናንተ እርሱን አታውቁትም።**

29. **እኔ እርሱን አውቀዋለሁ፤ እኔ ከእርሱ ዘንድ ስለ መጣሁና እርሱ ስለ ላከኝ ነው።"**

30. **ስለዚህ እነርሱ ኢየሱስን ሊይዙት ሞከሩት ነበር፣ ነገር ግን ጊዜው ገና ስላልደረሰ ማንም አልያዘውም።**

31. **ሆኖም ከሕዝቡ ብዙዎቹ በእርሱ አመኑ፣ እነርሱ እንዲህ አሉ፣ "ክርስቶስ ሲመጣ ይህ ሰው ካደረጋቸው ተአምራት የበለጠ ያደርጋልን**?"

32. **ሰዎቹ ስለ ኢየሱስ በሹክሹክታ ሲነጋገሩ ፈሪሳውያን ሰሙ፣ ስለዚህ የካህናት አለቆችና ፈሪሳውያንም እንዲይዙት የቤተ መቅደስ ጠባቂዎችን ላኩ።**

33. **በዚያን ጊዜ ኢየሱስ እንዲህ አለ፣ "እኔ ከእናንተ ጋር ጥቂት ጊዜ እቈያለሁ፣ ከዚያ በኋላ ወደ ላከኝ እሄዳለሁ፣**

34. **እናንተ እኔን ትፈልጉኛላችሁ፣ ግን አታገኙኝም፤ እኔ ወዳለሁበት፣ እናንተ መምጣት አትችሉም።"**

35. **ስለዚህ እርስ በርሳቸው እንዲህ ተባባሉ፣ ይህ ሰው ወዴት ሊሄድ እኛ እንዳናገኘው ቢያስብ ነው**? **ምናልባት በግሪኮች መካከል ወደ ተበተኑት አይሁድ ዘንድ ሄዶ አሕዛብን ያስተምር ይሆን**?

36. **'እናንተ እኔን ትፈልጉኛላችሁ፣ ነገር ግን አታገኙኝም፤ እኔ ወዳለሁበት እናንተ ልትመጡ አትችሉም' ሲል ምን ማለቱ ነው**?"

**ቁ**. 28,29 በመጀመሪያ ኢየሱስ ከእግዚአብሔር ጋር ነበር። ኢየሱስ ከእግዚአብሔር ዘንድ የተላከ ሰው ነው። (ዮሐ. 1፥1) ነገር ግን አይሁዶች ኢየሱስን አላወቁትም። እኛ በቃሉ በኩል ከእግዚአብሔር ጋር የቅርብ ግንኙነት አለን። እኛ የእውነተኛ መንፈስ ቅዱስ እርዳታን ተቀብለን እግዚአብሔርን በቅርብ አወቀን ይሁን?

**ቁ**. 30 አይሁዶች ኢየሱስን ለመያዝ ጥሩ ጊዜ ነበራቸው። ነገር ግን ማንም ኢየሱስን አልያዘም። ምክንያቱም የእግዚአብሔር ጊዜ ስላልሆነ ነው። እኛን እግዚአብሔር ሁልጊዜ እንዲጠብቅ እንጸልያለን።

**ቁ**. 33,34,36 ኢየሱስ ከራሱ ሰዎች ጋር ጥቂት ኖሮ ወደ እግዚአብሔር ተመልሷል። ይህ ከመስቀል ሞት በኋላ ተነስቶ ወደ ሰማይ በመሄዱ በኩል የእግዚአብሔር ልጅ ወደ ክብር ቦታ በመወሰዱ አዳነ ማለት ነው። አሁን ኢየሱስ የእግዚአብሔርን ሥራ ፈጽሞ ወደ አባቱ ተመልሷል። ወደ ሰማይም ሄዶ መንፈስ ቅዱስን ወደ እኛ ልኮ ከእኛ ጋር እንዲኖር አድርጓል። (ዮሐ. 16፥7)

**ቁ**.25-27 አይሁዶች የኢየሱስን አገር ስለሚያውቁ ኢየሱስን መሲሕ እንደሆነ አላሰቡትም። እኛ ደግሞ ትንሽ የመጽሐፍ ቅዱስ እውቀት ስላለን ኢየሱስን እንዳንሳሳት ጥንቃቄ እናድርግ!

**እንጸልይ፦** ጌታ ሆይ፤ የእግዚአብሔርን ቃል ስናነብ አጥብቀን በማወቅና የቅርብ የወዳጅነት ግንኙነት እንዲኖረን እርዳን። አሜን!

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ**? **ማን ነው**?

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ** (**በስራ ላይ ማዋል**)

7. **ፀሎት**

25. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 7፥37−52 **ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፡− የሕይወትን ውሃ እንጠጣ**

37. **የበዓሉ መጨረሻ በሆነው በታላቁ ቀን ኢየሱስ ቆመና ድምፁን ከፍ አድርጎ እንዲህ አለ፣ “ማንም የተጠማ ቢኖር ወደ እኔ ይምጣና ይጠጣ፣**

38. **ማንም በእኔ የሚያምን፣ ቅዱስ መጽሐፍ እንዳለ፣ የሕይወት ውሃ ምንጭ ከውስጡ ይፈልቃል።”**

39. **ይህንንም የተናገረው በእርሱ የሚያምኑ ስለሚቀበሉት ስለ መንፈስ ቅዱስ ነበር፣ ምክንያቱም ኢየሱስ ገና ስላልከበረ፣ ለሰዎች መንፈስ ቅዱስ ገና አልተሰጠም ነበር።**

40. **ከሕዝቡ አንዳንዶቹ ይህን ቃል ሰምተው እንዲህ አሉ። “ይህ ሰው ይመጣል በእርግጥ ነቢዩ ነው”**

41. **ሌሎችም፣ “እርሱ ክርስቶስ ነው” አሉ። ሌሎች ደግሞ እንዲህ አሉ፣ “ክርስቶስ ከገሊላ እንዴት ሊመጣ ይችላል?**

42. **መጽሐፍ፣ ክርስቶስ ከዳዊት ዘር፣ ዳዊትም ከኖረበት ከቤተልሔም እንደሚመጣ ይናገር የለምን?” አሉ።**

43. **ስለዚህም በኢየሱሰ ምክንያት በሕዝቡ መካከል መለያየት ሆነ፣** 44. **ከእነርሱም አንዳንዶቹ ሊይዙት ፈልገው ነበር፣ ነገር ግን ማንም አልያዘውም።** 45. **ከዚህ በኋላ የቤተ መቅደስ ጠባቂዎቹ፣ ወደ ካህናት አለቆችና ወደ ፈሪሳውያን ተመልሰው ሄዱ፣ እነርሱም ጠባቂዎቹን፣ “ለምን አላመጣችሁትም?” አሉአቸው።**

46. **ጠባቂዎቹም፣ “እንደዚህ ሰው፣ ከቶ ማንም ተናግሮ አያውቅም” ሲሉ መለሱ።**

47. **እንግዲህ ፈሪሳውያን እንዲህ ሲሉ መለሱ፣ “እናንተም ደግሞ ተሳሳታችሁን?**

48. **ለመሆኑ ከባለ ሥልጣኖች ወይም ከፈሪሳውያን በእርሱ ያመኑ አሉን?**

49. **ነገር ግን ይህ የሙሴን ሕግ የማያውቅ ሕዝብ በእርግጥ የተረገመ ነው።”**

50. **ከዚህ በፊት ወደ ኢየሱስ ሄዶ የነበረውና ከፈሪሳውያን አንዱ የሆነው ኒቆዲሞስ እንዲህ አላቸው፣**

51. **“በሕጋችን አስቀድሞ አንድን ሰው ሳይሰማለትና ምን እንዳደረገ ሳይታወቅ ይፈረድበታልን?”**

52. **እነርሱም መለሱ አሉት። “አንተም ደግሞ ከገሊላ ነህን? ነቢይ ከገሊላ እንደማይነሣ መርምረህ ተረዳ!”**

**ቁ**. 37−39　　　ኢየሱስ ለተጠሙ ሰዎች የሕይወትን ውሃ አብዝቶ የሚሰጥ ሰው ነው። አይሁዶች በዳስ በዓል መጨረሻ ሌሊት ከሰሌሆም ኩሬ ውሃን በማምጣት በቤተ መቅደስ መሰዊያ ላይ በማፍሰስ ስራዓት ቅዳሴ ያደርጋሉ። በሰዓቱም መጨረሻ ጊዜም ይፈስሳል ብለው ይጠባበቃሉ። ነገር ግን ኢየሱስ ለዓለም ራሱ ውሃውን የሚሰጥ ሰው መሆኑን ተናገረ። ይህ ማለት ኢየሱስን ለሚያምኑ ሰዎች የሕይወትን ውሃ እንደ ወንዝ መንፈስ ቅዱስን ሞልቶ ይሰጣቸዋል ማለት ነው።

እኛ ለሕይወታችን እንደ ወንዝ የሚፈስ የመንፈስ ቅዱስ ሥራ እንዲሰጠን እንጸልያለን።

**ቁ**. 46 ኢየሱስ ኃይለኛ ትምህርት እያስተማረ ቤተ መቅደስን ለሚጠብቅ ዘበኛ የጥብቅ ስሜትን ገለጸ። የኢየሱስን ትምህርት የሚሰሙ ሰዎች በኢየሱስ ትምህርት ላይ አንዳንድ አስተያየቶችን ተናገሩ። እነርሱ "እንደ ኢየሱስ የሚናገር ሰው አላየንም" ብለው ተናገሩ። እኛ የእግዚአብሔርን ቃል ስናስብ ምን ዓይነት ስሜት ይሰማናል?

**ቁ**. 40−43,52　　　ኢየሱስ በገሊላ ብዙ ሥራወችን ሠርቶ የነብያትን ትንቢት ፈጸመ። ነገር ግን ሰዎች ኢየሱስን በገሊላ አጠገብ ተገናኝተው ማስረጃ የሌለውን ፍርድ በመስጠት መሰሁን አላወቁትም። እኛ ደግሞ ጌታን አይተን ማስረጃ የሌለው ፍርድ በመስጠት አድሎ አደረግን?

**ቁ**.45−49　ፈሪሳዊያን ሕግን የማያውቁ ኢየሱስን የሚያምኑ ሰዎችን ደንቆሮና የተገረመ ነው አሉ። እኛ እውቀት በማጣት ምክንያት የሌሎች ሰዎችን እምነት ፈረድን?

**እንጸልይ፦ ጌታ ሆይ፤ እንደ ወንዝ ሞልቶ የሚፈስ የሕይወትን ውሃ እንድትሰጥና በሕይወታችንም ይህ ወንዝ እንዲበዛ እርዳን። አሜን!**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

## 26. የንባብ ክፍል ዮሐንስ 7፥53–8፥11 ወር፡ ቀን፡

## ርዕስ፡– እኔ የምኮንን አይደለውም

**ዮሐንስ** 7፥53. እያንዳንዱም ወደ ቤቱ ሄደ።

**ዮሐንስ** 8፥1. ነገር ግን ኢየሱስ ወደ ደብረ ዘይት ሄደ።

2. በማግስቱም ጠዋት በማለዳ ወደ ቤተ መቅደስ ተመልሶ መጣ፣ ሕዝቡም ሁሉ ወደ ኢየሱስ ተሰበሰበ፣ ኢየሱስም ተቀምጦ ያስተምር ነበር። 3. የሕግ መምህራንና ፈሪሳውያን ስታመነዝር የተያዘች ሴት አመጡና በሕዝቡ ፊት አቆሙአት። 4. ኢየሱስን እንዲህ አሉት፣ "መምህር ሆይ፣ ይህች ሴት ስታመነዝር ተያዘች፣

5. ሙሴ በሕጉ እንደዚች ያሉ ሴቶች በድንጋይ እንድትሞት አዞናል፣ አንተስ ስለ እርስዋ ምን ትላለህ?"

6. እነርሱ ይህን ጥያቄ ያቀረቡለት፣ ኢየሱስን የሚከሱበት ምክንያት ለማግኘት ሲፈትኑት ነው። ኢየሱስ ጐንበስ ብሎ በጣቱ በመሬት ላይ ይጽፍ ጀመር። 7. እነርሱ ደጋግመው በጠየቁት ጊዜ ኢየሱስ ቀና እንዲህ ብሎ አላቸው፣ "ከእናንተ መካከል ኃጢአት የሌለበተ እርሱ አስቀድሞ ድንጋይ በእርስዋ ላይ ይጣል!"።

8. ከዚህም በኋላ ኢየሱስ እንደገና ጐንበስ ብሎ በምድር ላይ ጻፈ።

9. እነርሱም ይህን በሰሙ ጊዜ ከሽማግሌዎች ጀምሮ ሁሉም አንድ በአንድ ከዚያ ወጡ፣ ስለዚህ ኢየሱስ በመካከል ቆማ ከነበረችው ሴት ጋር ብቻ ቀረ።

10. ከዚህ በኋላ ኢየሱስ ቀና እንዲህ ብሎ አላት፣ "አንቺ ሴት ከሳሾችሽ የት አሉ? የፈረደብሽ ማንም የለምን?"።

11. እርስዋም እንዲህ አለች፣ "ጌታ ሆይ! ማንም የለም" ኢየሱስም እንዲህ አላት፣ "እኔም አልፈርድብሽም፣ ሂጂ፣ ከእንግዲህ ዳግመኛ ኃጢአት አትሥሪ!"

**ቁ**. 1–2 ኢየሱስ በቀን ቤተ መቅደስ ውስጥ እያስተማረ በሌሊት በወይራ ተራራ ላይ ይጸልያል። (ሉቃ. 21፥37,38) ራሱንም ለመግደል ሴራ በሚያደርጉት መካከል ኢየሱስ በየቀኑ ያስተምርና ይፀልይ ነበር። ከዚህ የተነሣ ኢየሱስን የእኛ አካባቢና ሁናቴ እንደማይለውጥ ትምህርት አገኘን።

**ቁ**. 6–9 ኢየሱስ አመንዝራ ሴትን ለሚኮኑኑት ሰዎች በመጀመሪያ የራሳቸውን ኃጢአት እንዲመረምሩ ተናገራቸው። ኢየሱስ የሰዎችን የጎሊና ጨለምተኝነትን ያያል። እኛ ደግሞ ሌሎች ሰዎችን ከመፍረድ በፊት ራሳችንን ልንመረምር ያስፈልጋል።

**ቁ.** 10−11 **"እኔም አልፈርድብሽም ሂጂ ከአሁንም ጀምሮ ደግመሽ ኃጢአት አትሥሪ"** (**ዮሐ.** 8፥10−11) **ብሎ ለሴትየዋ ሳይፈርድባት ምሕረትን ሰጠ። ለአንተም፣ ላንቺም፣ ለእኔም ለሁላችንም እኔም አልፈርድባቹሁም ሂዱ ከአሁን ጀምሮ ደግማችሁ ኃጢአት** "**አትሥሩ**" **ብሎ አንድ ዓይነት የፀጋ ቃል ይሰጣል።**

**ቁ.**3−6 ***የሕግ መሪዎችና ፈሪሳዊያን ኢየሱስን ለመፈተን "የሙሴ ሕግ እንደዚህ ዓይነት በደል የሠሩ ሰዎችን በድንጋይ ወግሮ እንዲገድል ያዘናል። አንተስ ምን ትላለህ?" ብለው ጠየቁት።***

***ዛሬ እኛን መጽሐፍ ቅዱስን የምናነብ የምንሰብክ ቤተ ክርስቲያንን የምንመራ ሰዎች ወንጌላዊያን፣ መጋቢያን እንዲሁም ዘማሪዎች በሙሉ እንደ ፈሪሳዊያንና እንደ ሕግ መሪዎች ኢየሱስን በሥህተት ፈትነን ይሆን?***

**እንጸልይ፦ ጌታ ሆይ፣ እኛ ሁልጊዜ የቤትህን *ሥራ* እየሠራን ሌሎች ሰዎችን በስህተት እንዳንኮንን እርዳን። አሜን!**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

## 27. የንባብ ክፍል ዮሐንስ 8፥12-20 ወር፦ ቀን፦

## ርዕስ፦ ኢየሱስ የዓለም ብርሃን ነው

12. እንደገናም ኢየሱስ ለሰዎቹ እንዲህ ሲል ተናገራቸው፣ "እኔ የዓለም ብርሃን ነኝ፣ እኔን የሚከተል ሁሉ በጨለማ አይመላለስም፣ የሕይወትም ብርሃን ያገኛል"

13. ፈሪሳውያንም እንዲህ አሉት፣ "አንተ ስለ ራስህ ትመሰክራለህ፣ ምስክርነትህ እውነት አይደለም"

14. ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰላቸው፣ "እኔ ስለ ራሴ ብመሰክር ከየት እንደ መጣሁ፣ ወዴት እንደምሄድ ስለማውቅ ምስክርነቴ እውነት ነው፣ ነገር ግን እናንተ ከየት እንደ መጣሁ ወይም ወዴት እንደሄድ አታውቁም።

15. እናንተ በሥጋዊ አስተሳሰብ ትፈርዳላችሁ፣ እኔ በማንም አልፈርድም።

16. ብፈርድም፣ ፍርዴ እውነት ነው፣ ምክንያትም እኔ ብቻዬን ስለማልፈርድ ነው፣ የላከኝ አብ ከእኔ ጋር ስለ ሆነ፣

17. የሁለት ሰዎች ምስክርነት እውነት እንደ ሆነ በሕጋችሁ ተጽፎአል።

18. እኔ ስለ ራሴ እመሰክራለሁ፣ የላከኝ አብም ስለ እኔ ይመሰክራል።"

19. በዚያን ጊዜ እነርሱ ሲሉ ጠየቁት፣ "አባትህን የት ነው?" ኢየሱስም ሲል መለሰላቸው፣ "እናንተ እኔን ወይም አባቴን አታውቁም፣ እኔን ብታውቁኝ ኖሮ አባቴንም ባወቃችሁ ነበር!"

20. ኢየሱስ ይህን ቃል የተናገረው በቤተ መቅደሱ ግቢ፣ በግምጃ ቤት አጠገብ ሲያስተምር ነበር፣ ጊዜው ገና ስላልደረሰ ማንም አልያዘውም።

ቁ. 12 ኢየሱስ ለጨለማ ዓለም ብርሃን ሆኖ መጥቶ ጨለማውን አውጥቶ እውነተኛ ሕይወትን ይሰጣል። እኛ ኢየሱስን ተቀብለን በዚህ ብርሃን መካከል እየኖርንና እግዚአብሔር የሰጠውን የዘላለም ሕይወትን እንከፋፈላለን።

ቁ.14-18 የኢየሱስ ምስክርነት እውነት ነው። የኢየሱስ ፍርድ እንደ ሰው ልማድ ፈሪሳዊያንም እንደሚፈርዱት አይደለም ምክንያቱም ኢየሱስ ብቻውን ከእግዚአብሔር ጋር የሚፈርድ ነው። ደግሞም በሙሴ ሕግ የሁለት ሰው ምስክርነት ይጸናል። (ዘዳ. 17፥6) የኢየሱስ ምሰክርነትና የእግዚአብሔር ምሰክርነት ስላለው የኢየሱስ ምስክርነት እውነት ነው።

**ቁ**. 19 **ኢየሱስ እግዚአብሔርን የሚያሳውቅና ወደ አብ የሚወስደው መንገድ ነው። ከኢየሱስ በቀር እግዚአብሔርን የሚያውቅ ከቶ የለም። እኛ ደግሞ ኢየሱሱን ካልተገናኘን ኢየሱስ የራሱን ድምፅ አያሰማም እግዚአብሔርንም አያሳውቅም ወደ ሰማይም አይወስደንም።**

**ቁ**. 20 **ኢየሱስ የእግዚአብሔር ጊዜና የራሱን ሥራ ያውቃል። ስለዚህ ሕይወቱን ለመግደል ሰዎች ሴራ ሲያደርጉ ኢየሱስ ሰዎችን ማስተማሩንና መጸለዩን አላቆመም። እኛ በእግዚአብሔር ጊዜ እንዴት እየተቆጣን ነው? የእግዚአብሔርንስ ጊዜ በሕይወታችን እናውቃለን?**

**እንጸልይ፡- ጌታ ሆይ፣ በጨለማ ውስጥ ያሉትን ጐረቤቶቻችንን ወደ ቤትህ ወደ ብርሃን እንድናመጣና እኛም በብርሃን ውስጥ እንድንመላለስ እርዳን። አሜን!**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

28. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 8፥21-30 **ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፡- በእኔ የማያምኑ**

21. **ኢየሱስም እንደገና እንዲህ አላቸው፣ "እኔ እሄዳለሁ፣ እናንተም ትፈልጉኛላችሁ፣ ነገር ግን በኃጢአታችሁም ትሞታላችሁ፣ እኔ ወደምሄድበት እናንተ ግን ልትመጡ አትችሉም"**

22. **አይሁድም እንዲህ አሉ፣ " 'እኔ ወደምሄድበት ልትመጡ አትችሉም' ማለቱ ራሱን ሊገድል ይሆን?"**

23. **ኢየሱስም እንዲህ አላቸው፣ "እናንተ ከታች ናችሁ፣ እኔ ከላይ ነኝ፣ እናንተ ከዚህ ዓለም ናችሁ፣ እኔ ከዚህ ዓለም አይደለሁም።**

24. **እንግዲህ እኔ ለእናንተ በኃጢአታችሁ እንደምትሞቱ አልኳችሁ፣ እኔን በክርስቶስ ባታምኑ በኃጢአታችሁ ትሞታላችሁ።"**

25. **እነርሱም አሉት፣ "አንተ ማን ነህ?" ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰላቸው፣ "ከመጀመሪያ ለእናንተ የነገርኳችሁ እኔ እርሱ ነኝ፣**

26. **ስለ እናንተ የምናገረውና የምፈርደው ብዙ ነገር አለኝ፣ የላከኝ እውነተኛ ነው፣ ነገር ግን እኔ ከእርሱ የሰማሁትን ለዓለም እናገራለሁ።"**

27. **እነርሱም ኢየሱስ ስለ የእግዚአብሔር አብ እንደ ተናገራቸው አላስተዋሉም።**

28. **ስለዚህ ኢየሱስ እንዲህ አላቸው፣ "እናንተ የሰው ልጅን ከፍ ባደረጋችሁት ጊዜ፣ እኔ ክርስቶስ እንደ ሆንሁና አብ ያስተማረኝን እንደምናገር፣ በራሴም ፈቃድ ምንም እንደማላደርግ ታውቃላችሁ፣**

29. **የላከኝ ከእኔ ጋር ነው፣ እኔ ሁልጊዜ እርሱን ደስ የሚያሰኘውን ስለማደርግ ብቻዬን አልተወኝም።"**

30. **ኢየሱስ ይህን በተናገረ ጊዜ ብዙ ሰዎች በእርሱ አመኑ።**

**ቁ**. 23,24 **ኢየሱስ ከዓለም ሳይሆን ከሰማይ የሆነ ነው። ኢየሱስ ሲናገር "እኔ እኔ ነኝ"** (**እኔ ያለሁና የምኖር ነኝ**) (**ዘጸ፡**3፥14) **ብሎ ተናገረ። ኢየሱስ በውሃ ላይ እየሄደ "እኔ ነኝ አትፍሩ" አላቸው። ደግሞም "እኔ የሕይወት እንጀራና የሕይወት ብርሃን ነኝ" አለ። ስለዚህ ኢየሱስ የእኛ ኃጢአትን ይቅር ለማለት ከሰማይ የመጣውን ጌታ አድርገን አመንን**?

**ቁ**. 26 ኢየሱስ ራሱን ከላከው ከእግዚአብሔር ሰምቶ ለዓለም ይናገራል። ኢየሱስን ለዓለም የላከው እግዚአብሔር እውነተኛ ነው። ስለዚህ የኢየሱስ ቃል የእውነት ቃል ነው። በየቀኑ እኛን እንዲለውጥ መጽሐፍ ቅዱስን በመስማትና በማንበብ እናደርጋለን።

**ቁ**. 28 አይሁዶች ኢየሱስን በመስቀል ላይ እንዲሞት አደረጉ። ነገር ግን ኢየሱስ በመስቀል ላይ ክብርን ተቀብሎ ራሱን ለሚያምኑ የዘላለም ሕይወት ሰጠ። (ዮሐ፥ 3፥16) በየቀኑ እኛ በመስቀል ላይ ከፍ በማለት የኢየሱስን ሞትና ትንሣኤ ትኩረት ሰጥተን እያሰብን ነን?

**ቁ**. 29 ኢየሱስ ሁል ጊዜ እግዚአብሔርን የሚያስደስት ሥራ በማድረግ እስከመስቀል ሞት ድረስ ታዘዘ። እግዚአብሔር ኢየሱስን ብቻውን አልተወውምና ሁል ጊዜ ከእርሱ ጋር አለ። ዛሬ እኛ ለቃሉ ታዝዘን ስንኖር እግዚአብሔር ሁል ጊዜ ከእኛ ጋር አለ።

**ቁ**. 22,25,27 ኢየሱስ ለአይሁዶች ብዙ ጊዜ ተናገራቸው። ነገር ግን አይሁዶች "አንተ ማን ነህ?" ብለው ጠየቁ። ምክንያቱም ልባቸው በክፋት የተሞላ ስለሆነ ኢየሱስን አላዩም (ኢሳ፥ 6፥10) እኛ ቃሉን በምንሰማበትና በምናነብበት ጊዜ ልባችን በደንብ እንዲያስተውል እንጸልያለን።

**እንጸልይ፡- ጌታ ሆይ፤ በየቀኑ እኛ የጌታን ቃል በምንሰማበትና በምናነብበት ጊዜ ይበልጥ ቃሉን እንድናውቅና በደስታ እንድንታዘዝ እርዳን። አሜን!**

1. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ

2. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት

3. እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?

4. የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና

5. ትምህርት

6. ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)

7. ፀሎት

29. **የንባብ ክፍል  ዮሐንስ** 8፥31-41 **ወር፡  ቀን፡**

**ርዕስ፡- አንተ የማን ልጅ ነህ**?

31. **እንግዲህ ኢየሱስ በእርሱ ያመኑትን አይሁድ እንዲህ አላቸው፤ “እናንተ በቃሌ ብትኖሩ በእውነት ደቀ መዛሙርቴ ናችሁ፤**

32. **እውነትን ታውቃላችሁ፤ እውነትም እናንተን ነጻ ያወጣችኋል።”**

33. **እነርሱም መልሰው፣ “እኛ የአብርሃም ዘር ነን፤ ከቶ ለማንም ባሪያዎች ሆነን አናውቅም፤ ታዲያ፣ ‘አንተ ለእኛ ነጻ ትወጣላችሁ’ እንዴት ትላለህ**? **አሉት።**

34. **ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰላቸው፤ “እኔ በእውነት እላችኋለሁ፤ ኃጢአት የሚያደርግ ሁሉ የኃጢአት ባሪያ ነው፤**

35. **ባሪያ ለዘላለም በቤተሰቡ ውስጥ አይኖርም፤ ነገር ግን ልጅ በቤት ለዘላለም ይኖራል።**

36. **ስለዚህ ወልድ እናንተን ነጻ ካወጣችሁ፣ እናንተ በእውነት ነጻ ትሆናላችሁ።**

37. **እኔ እናንተ የአብርሃም ዘር መሆናችሁን አውቃለሁ፤ ነገር ግን እናንተ ቃሌን ስለማትቀበሉ ልትገድሉኝ ትፈልጋላችሁ።**

38. **እኔ በአባቴ ዘንድ ያየሁትን እናገራለሁ፤ እናንተም ከአባታችሁ የሰማችሁትን ታደርጋላችሁ።**

39. **እነርሱም፣ “አባታችንስ አብርሃም ነው” ብለው መለሱለት። ኢየሱስም እንዲህ አላቸው፤ “የአብርሃም ልጆችስ ብትሆኑ፣ እናንተ ደግሞ አብርሃም የሠራውን በሠራችሁ ነበር፤**

40. **እኔ ከእግዚአብሔር የሰማሁትን እውነት ነገርኋችሁ፤ ነገር ግን አሁን እናንተ ልትገድሉኝ ትፈልጋላችሁ፤ አብርሃም እንዲህ አላደረገም።**

41. **እናንተ የምትሠሩት የአባታችሁን ሥራ ነው።” እነርሱም ለኢየሱስ እንዲህ ሲሉ መለሱለት፣ “እኛ በዝሙት የተወለድን አይደለንም፤ አባታችንም አንዱ እግዚአብሔር ብቻ ነው”**

**ቁ**. 32,34-36  **ኢየሱስ ለእኛ ከኃጢአት ነፃነትን ሰጠ። ኢየሱስ የሰጠው ነፃነት እኛ የምንፈልገውን ማንኛውንም ነገር የሚያደርግ ነፃነት አይደለም። ነገር ግን ኢየሱስ የሰጠው ነፃነት በኢየሱስ ቃል እንድንኖር የሚያደርግ ነፃነት ነው። እኛ ይህንን ነፃነት አሁን ቀምሰናል**? **አሁን እኛን ያሠረን የትኛው ኃጢአት ነው**?

**ቁ**. 37–41 **አይሁዶች ኢየሱስን ለመግደል እንደሚፈልጉ ለእነርሱ የዲያብሎስ ልጅ ገለጸ። እውነተኛ የአብርሃም ልጆች ቢሆኑ እንደዚህ አይነት ሥራ አይሰሩም። እኛ በመንፈስ የማንም ልጅ የሃይማኖትንም ግንኙነት፣ የቤተሰብና የቤተክርስቲያን ሰብስብ አይደለንም። ነገር ግን እኛ የማን ተከታዮች እንደሆንንና በቃሉ የምንኖር ወይም በኃጢአት መካከል እንደምንኖር ማንነታችን ይገልፃል። አንተ የማን ልጅ ነህ? እናንተ የማን ልጆች ናችሁ?**

**ቁ**. 33–36 **አይሁዶች በራሳቸው ሀሳብ "እኛ የአብርሃም ልጆች ነን" ብለው ይጠነቀቃሉ። ነገር ግን እውነተኛ እግዚአብሔር የላከው የኢየሱስ ቃል አልገባቸውም። ምክንያቱም እነርሱም ለኃጢአት ባሪያ ስለመሰላቸው ነው። እኛ ደግሞ ዝነኛ ቤተክርስቲያንና የእምነት ክርሰቲያኖች ሆነን ስንጠግብ በየቀኑ በቃል ውስጥ ባለመቆየት ገና በኃጢአት መካከል እንኖራለን።**

**እንጸልይ፡– ጌታ ሆይ፤ እኛ በየቀኑ እንደ ቃሉ እንድንኖር እርዳን። አሜን!**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

**30. የንባብ ክፍል ዮሐንስ 8፥42-51 ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፡- ኢየሱስ ከአብርሃም የሚበልጥ ሰው ነው**

42. ኢየሱስም እንዲህ አላቸው፣ "እግዚአብሔር አባታችሁ ቢሆንማ፣ እኔን በወደዳችሁኝ ነበር፣ እኔ ወደዚህ የመጣሁት ከእግዚአብሔር ዘንድ ነው፣ እግዚአብሔር ላከኝ እንጂ በገዛ ራሴ አልመጣሁም።

43. እናንተ ለምን የምናገረውን አታስተውሉም? ምክንያቱም እናንተ ቃሌን ለመስማት ስለማትችሉ ነው።

44. እናንተ የአባታችሁ የዲያብሎስ ልጆች ናችሁ፣ የአባታችሁንም ፍላጎት ለመፈጸም ትሻላችሁ። እርሱ ከመጀመሪያ ነፍሰ ገዳይ ነበር፣ በዲያብሎስ እውነት ስለሌለ በእውነት አልቆመም፣ ዲያብሎስ ሐሰተኛና የሐሰት አባት ስለ ሆነ ሐሰት በሚናገርበት ጊዜ ከገዛ ራሱ አውጥቶ ይናገራል። 45. ነገር ግን እኔ እውነት ስለምናገር አታምኑኝም። 46. ከእናንተ 'ኃጢአተኛ ነህ' ብሎ የሚወቅሰኝ ማን ነው? እኔ እውነት የምናገር ከሆነ፣ ታዲያ፣ ለምን አታምኑኝም?

47. ከእግዚአብሔር የሆነ የእግዚአብሔር ቃል ይሰማል፣ እናንተ የእግዚአብሔር ቃል የማትሰሙት ከእግዚአብሔር ስላልሆናችሁ ነው።" 48. አይሁድ መልሰው እንዲህ አሉት፣ "አንተ ሳምራዊ ነህ፣ ጋኔንም አለብህ፣ ማለታችን ትክክል አይደለምን?" 49. ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰላቸው፣ "እኔ ጋኔን የለብኝም፣ ነገር ግን አባቴን አከብራለሁ፣ እናንተም እኔን ታዋርዱኛላችሁ። 50. እኔ የራሴን ክብር አልፈልግም፣ የእኔን መከበር የሚፈልግና የሚፈርድ ሌላ አለ።

51. እኔ በእውነት እላችኋለሁ፣ ቃሌን የሚጠብቅ ፈጽሞ አይሞትም።"

**ቁ.** 42 ኢየሱስ ከእግዚአብሔር የተወለደና ከእግዚአብሔር የተላከ ሰው ነው። የእግዚአብሔር ልጆች ተብለው የሚጠሩ ሰዎች ኢየሱስን ይወዳሉ። ነገር ግን አይሁዶች ኢየሱስን ለይቶ በማስቀረት ለመግደል ሞከሩ። እኛን ከኃጢአት ለማዳን የመጣውን ኢየሱስን እንወደዋለን?

**ቁ.** 43-47 ኢየሱስ እውነትን ተናገረ። በእግዚአብሔር ውስጥ ያለው ሰው የእግዚአብሔርን ቃል የሚሰማ የሚያምን ነው። ነገር ግን በውሸት አባት በሰይጣን ውስጥ የሚኖሩ ሰዎች የእውነትን ቃል አይሰሙምና ከሰሙት በኋላ አያስተውሉም። እኛ በማን ውስጥ አለን?

**ቁ**. 48−51 **ኢየሱስ ለራሱ ክብርን አልተቀበለም። እግዚአብሔርን አከበረ። ይህ የኢየሱስን ሥራ እግዚአብሔር ፈረደ። አይሁዶች በዓለም ትዕይንት ኢየሱስን ፈረዱና ተቃወሙ። ምክንያቱም ራሳቸው ስለ እግዚአብሔር አለማወቃቸውን ገለጹ። እኛ ስለ ኢየሱስ ምን ዓይነት ትዕይንት አሳየን**?

**ቁ**. 43,47 **የእግዚአብሔርን ቃል ሰምቶ የማያስተውል ከእግዚአብሔር አልተወለደም። ከላይ የሚመጣው ያለ መንፈስ ቅዱስ ሥራ የእግዚአብሔርን ቃል ማስተዋል አይቻልም። ስለዚህ እኛ የእግዚአብሔርን ቃል ስናነብ ሁል ጊዜ ከላይ የሚመጣው መንፈስ ቅዱስ ጥበብን እንዲሰጠን እንጸልያለን።**

**እንጸልይ፦ ጌታ ሆይ፤ የእኛ ጠንካራና አስቸጋሪ ሕይወት የእግዚአብሔርን ቃል እንዲጠብቅና እንዲታዘዝ እርዳን፤ አሜን**!

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ**? **ማን ነው**?

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ** (**በስራ ላይ ማዋል**)

7. **ፀሎት**

31. **የንባብ ክፍል** **ዮሐንስ** 8፥52-59 **ወር፡** **ቀን፡**

**ርዕስ፡- አብርሃም የሚመጣውን መሲሑን ይጠባበቃል**

52. **አይሁድ እንዲህ አሉት፣ "እኛ አንተ ጋኔን እንዳለብህ አሁን አወቅን፣ አብርሃም እንኳ ሞቶአል፣ ነቢያትም ሞተዋል፣ ነገር ግን አንተ 'ቃሌን የሚጠብቅ አይሞትም' ትላለህ፣**

53. **አንተ ከሞተው ከአባታችን ከአብርሃም ትበልጣለህን**? **ነቢያት ሞተዋል፣ ታዲያ፣ አንተ ራስህን ማንን ታደርጋለህ**?"

54. **ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰ፣ "እኔ ራሴን ባከብር፣ ክብሬ ከንቱ ነው፣ እኔን የሚያከብረኝ አባቴ ነው፣ እርሱም 'እናንተ አምላካችን' የምትሉት ነው።**

55. **እናንተ እርሱን አላወቃችሁትም፣ ነገር ግን እኔ አውቀዋለሁ፣ እኔ እርሱን አላውቀውም ብል፣ እንደ እናንተ ሐሰተኛ እሆናለሁ፤ ነገር ግን እኔ እርሱን አውቀዋለሁ፣ ቃሉንም እጠብቃለሁ።**

56. **የአባታችሁ አብርሃም የእኔን ቀን ለማየት ተስፋ በማድረግ ተደሰተ፣ አየም፣ ሐሤትም አደረገ።**"

57. **በዚህ ጊዜ አይሁድ እንዲህ አሉት፣ "አንተ ገና አምሳ ዓመት አልሆነህም፣ ታዲያ አንተ እንዴት አብርሃምን አይተሃል**!"

58. **ኢየሱስም እንዲህ አላቸው፣ "እኔ በእውነት እላችኋለሁ፣ አብርሃም ከመወለዱ በፊት እኔ ነበርኩ።**"

59. **ስለዚህ አይሁድ ሊወግሩት ድንጋይ አነሡ፣ ነገር ግን ኢየሱስ ተሰወረባቸውና ከቤተ መቅደስ ወጥቶ ሄደ።**

**ቁ**. 54,55 **ኢየሱስ ራሱ ክብር አልተቀበለም። ነገር ግን ለእግዚአብሔር ክብርን ሰጠ። ኢየሱስ ሁል ጊዜ እግዚአብሔርን አውቆና ለእግዚብሔር ቃል በመታዘዝ አባቱን አከበረ። እግዚአብሔር ደግሞ ለኢየሱስ አክብሮትን ሰጠ።** (**ዮሐ፡** 17፥4,5) **ዛሬ ለራሳቸው ክብርን ለመቀበል የማይፈልጉ ሰዎች፣ የእግዚአብሔርን ቃል በመጠበቅና የአባታቸውን ክብር የሚፈልጉ ሰዎች፣ ጌታ የክብር ልብስ መሸፈኛን ይሰጣቸዋል። እኛ ደግሞ ለጌታ ቃል በመታዘዝ በዚህ ክብር እንደሰታለን።**

**ቁ**. 56−58 **ኢየሱስ ከአብርሃም በፊት ያለው ለዘላለም የሚኖር ሰው ነው። "እኔ አለሁ" ማለት "እኔ እኔ ነኝ" ማለት ነው።** (**ዘጸ፡** 3፥14) **ይህ ማለት በሰማይና በምድር ያሉ ፍጥረታት ሁሉ ቢጠፉም ኢየሱስ ለዘላለም የሚኖር ነው ማለት ነው። እኛ ይህን ቃል ሰምተን ኢየሱስን ምን ለማድረግ አሰብን**?

**ቁ**. 52,53,59 **አይሁዶች ኢየሱስ ራሱ እኔ እግዚአብሔር ነኝ ያለውን ቃል ሰምተው እግዚአብሔርን ክፉ ቃል ሰደበ ብለው በኢየሱስ ላይ ድንጋይ ለመጣል ፈለጉ። በእርግጥ አይሁዶች የእግዚአብሔርን ልጅ ኢየሱስን ይሰድባሉ። እኛ ደግሞ እንደዚህ ዓይነት ሥራዎችን እውነት መሆናቸውን ልንመረምር ያስፈልጋል። እንጸልይ፦ ጌታ ሆይ፤ ኢየሱስ ፈጣሪ መሆኑን አውቀን በእምነት የምናደርገውን ሥራ እንድናደርግ እርዳን፤ አሜን**!

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ**? **ማን ነው**?

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ** (**በስራ ላይ ማዋል**)

7. **ፀሎት**

## 32. የንባብ ክፍል ዮሐንስ 9፥1−12 ወር፡ ቀን፡

## ርዕስ፡− ኢየሱስ ዕውር ሆኖ የተወለደውን ሰው ፈወሰ

1. ኢየሱስ በመንገድ ሲያልፍ ከተወለደ ጀምሮ ዕውር የሆነውን ሰው አየ።
2. ደቀ መዛሙርቱም ኢየሱስን እንዲህ ሲሉ ጠየቁት፣ ይህ ሰው ዕውር ሆኖ እንዲወለድ የማን ኃጢአት ምክንያት ነው? እርሱ ራሱ ወይስ ወላጆቹ?" 3. ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰ፣ "ይህ ሰው ዕውር ሆኖ እንዲወለድ በእርሱ ወይም በወላጆቹ ኃጢአት ምክንያት አይደለም፣ ነገር ግን ይህ የሆነው የእግዚአብሔር ሥራ በእርሱ እንዲገለጥ ነው።

4. ቀን ሳለ፣ የላከኝን ሥራ መሥራት አለብን፣ ማንም ሊሠራ የማይችልበት ሌሊት ይመጣል፣

5. በዓለም ሳለሁ፣ እኔ የዓለም ብርሃን ነኝ።"

6. ኢየሱስ ይህን ከተናገረ በኋላ፣ በምድር ላይ እንትፍ ብሎ በምራቁ ጭቃ አበጀ፣ በጭቃውም የዕውሩን ዓይኖች ቀባ።

7. ኢየሱስም እንዲህ አለው፣ "ሄደህ በሰሊሆም መጠመቂያ ታጠብ"። (ሰሊሆም "የተላከ" ማለት ነው።) ስለዚህ ሰውየው ሄዶ ታጠበና እያየ ተመለሰ። 8. በዚያን ጊዜ ጐረቤቶቹና ቀድሞ ሲለምን ያዩት የነበሩ ሰዎች እንዲህ አሉ፣ "ይህ ሰው ተቀምጦ ሲለምን የነበረው አይደለምን?"።

9. አንዳንዶቹም፣ "አዎ፣ እርሱ ነው!" አሉ፣ ሌሎችሞ "እርሱን ይመስላል እንጂ እርሱ አይደለም!" አሉ። ነገር ግን እርሱ "እኔው ነኝ!" አለ። 10. እነርሱም እንዲህ ሲሉ ጠየቁት፣ "ታዲያ፣ ዓይኖችህ እንዴት ተከፈቱ?"።

11. እርሱ እንዲህ መለሰ፣ "ኢየሱስ የሚሉት ሰው ጭቃ አድርጎ አይኖቼን ቀባኝ፣ 'ወደ ሰሊሆም ሄደህ ታጠብ' አለኝ፣ እኔም ሄጄ ታጠብሁና ለማየት ቻልሁ" ።

12. እነርሱም "ሰውየው አሁን የት አለ?" አሉት። እርሱም "እኔ አላውቅም" አላቸው።

ቁ. 1,3 ኢየሱስ የእግዚአብሔርን ክብር ለመግለጽ ዕውር የሆነውን ሰው ፈወሰ። ኢየሱስ ከመወለዱ ጀምሮ ዕውር የሆነውን ሰው ዓይኖች ከፍቶ ኃጢአቱን ይቅር አለ። ይህ ሥራ ዕውሩን መፈወሱ የራሱ ሰው አድርጎ መዋጀቱ ድንቅ ጸጋ ነው። ዕውሩን ፈውሶ የእግዚአብሔር ፈቃድ መፈጸሙን በእኛ በኩል ደግሞ የእግዚአብሔር መንግሥት ሥራ እንዴት ልናደርግ እንደሚገባ ያሳስበናል።

**ቁ.** 7 ኢየሱስ ዕውሩን ወደ ሰሎሆም መጥመቂያ ልኮ ፈወሰ። ሰሎሆም ማለት "የላከውን መቀበል" ማለት ነው። ኢየሱስ ራሱን የላከውን ፈቃድ ለመግለጽ ዕውሩን ወደ ሰሎሆም ላከ። የእግዚአብሔር ፈቃድ የሚታዘዝና የሚያደርግ ሰው ተአምራትን ያያል።

**ቁ.** 2 የደቀ መዛሙርቶች ሃሳብ የሰዎች ትግል ኃጢአት ውጤት ነው ብለው ያስባሉ። ነገር ግን በሽታ ወይም መጥፎ እድል የኃጢአት ውጤት ነው ብለው ማሰብ ትክክል አይደለም።

**ቁ.** 8–11 ወደ ሰሎሆም ሄዶ አይኖቹ የተከፈተው ዕውር ራሱ ለአከባቢው ሰዎች ስለ ኢየሱስ መሰከረ። እርሱ ኢየሱስን በትንሹ ካወቀ በኋላ የራሱ ሕይወት በግልጽ አጥርቶ አየ።

**እንጸልይ፡–** ጌታ ሆይ፤ እኛ በጨለማ ውስጥ ላሉ ሰዎች የወንጌልን ብርሃን እንድንመሰክር እርዳን፤ አሜን!

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

## 33. የንባብ ክፍል ዮሐንስ 9፥13-23 ወር፡ ቀን፡

## ርዕስ፡- የፈሪሳውያን ምርመራ

13. እነርሱም ዕውር የነበረውን ሰው ወደ ፈሪሳውያን ወሰዱት።

14. ኢየሱስ ጭቃ አድርጎ የሰውዬውን ዓይኖቹን የከፈተበት ቀን ሰንበት ነበረ።

15. ስለዚህ ፈሪሳውያንም እንዴት ማየት እንደ ቻለ እንደገና ጠየቁት። እርሱም እንዲህ አላቸው፣ "ኢየሱስ ዓይኖቼ ላይ ጭቃ ቀባኝ፣ እኔም ታጠብሁ፣ ከዚያም በኋላ ማየት ቻልሁ"።

16. ከፈሪሳውያን አንዳንዶቹ፣ "ይህ ሰው ሰንበትን ስለማያከብር ከእግዚአብሔር አይደለም" አሉ። ሌሎች ግን፣ "ኃጢአተኛ፣ እንዲህ ያሉትን ምልክቶች እንዴት ሊያደርግ ይችላል?" አሉ። በዚህ ምክንያት በመካከላቸው መለያየት ሆነ። 17. ስለዚህ እነርሱ ወደ ዕውር የነበረውን ሰው እንዲህ ሲሉ ደግመው ጠየቁት፣ "ዓይኖችህን ስለ ከፈተው ሰው፣ አንተስ ስለ እርሱ ምን ትላለህ?" እርሱም "ነቢይ ነው!" አለ።

18. አይሁድ ሰውየው ዕውር እንደ ነበረና እንዳየ አላመኑም ነበር፣ ስለዚህ እነርሱ ወደ ወላጆቹ ልከው እንዲህ ሲሉ ጠየቁአቸው። 19. "ዕውር ሆኖ ተወለደ የምትሉት ልጃችሁ ይህ ነው? ታዲያ አሁን እንዴት ማየት ቻለ?"

20. ወላጆቹም እንዲህ ሲሉ መለሱ፣ "ይህ ሰው ልጃችን መሆኑንና ዕውር ሆኖ መወለዱን እናውቃለን፣

21. ነገር ግን አሁን እንዴት እንደሚያይና ዓይኖቹንም ማን እንደ ከፈተለት እኛ አናውቅም። እርሱን ጠይቁት፣ እርሱ በዕድሜው ሙሉ ሰው ስለ ሆነ ስለ ራሱ መናገር ይችላል።"

22. ወላጆቹ ይህን ያሉት አይሁድን ስለ ፈሩ ነበር፤ ኢየሱስን፣ "ክርስቶስ ነው" ብሎ የመሰከረ ሁሉ ከምኵራብ እንዲባረር አይሁድ አስቀድመው ወስነው ስለ ነበር፣ 23. ስለዚህ ወላጆቹ፣ "እርሱ በዕድሜው ሙሉ ሰው ነው፣ እርሱን ጠይቁት" አሉ።

**ቁ.** 14 ኢየሱስ በሰንበት የዕውሩን አይኖች ፈውሶ በጨለማ ዓለም ውስጥ ላሉት ነፃነትን፣ እውነተኛ የእረፍት ቀንና ደስታን ሰጣቸው። ኢየሱስ የ38 ዓመት ህመምተኛውን በሰንበት ቀን ፈወሶ "የእኔ አባት እስካሁን ድረስ ይሰራል። እኔ ደግሞ እሠራለው።" ብሎ ተናገራቸው። ይህ ማለት ኢየሱስ የሰንበት ጌታ መሆኑን ይገልጻል።

(ዮሐ፡ 5፥17) እውነተኛ እረፍት ሕግን ከመጠበቅ ይልቅ ሕግን የሚፈጽም ኢየሱስን የሚያገኝ ይሆናል። ኢየሱስን ተቀብለህ በዚህ እረፍት ተደስተሃል?

**ቁ**. 15,21,22 ዕውሩ በፈሪሳውያን ፊት ደፍሮ ስለ ኢየሱስ እውነት ገለጸ። ነገር ግን የዕውሩ ወላጆች አይሁዶችን ስለፈሩ እውነቱን ለመመስከር ሸክሙን ለልጁ ተው። እኛ ደግሞ እንደ ዕውሩ ወላጆች ሰዎችን ፈርተን ስለ ኢየሱስ አልመሰከርንምን?

**ቁ**. 17,18 ዕውሩ ኢየሱስ ዓይኖቹን በሚፈውስበት ጊዜ በደንብ አላወቀም። ነገር ግን ቀስ በቀስ ኢየሱስ ማን እንደ ሆነ በትክክል እያወቀ ሄደ። ይህ የፈሪሳውያን ልዩነት መንፈሳዊ እውርነት ነው። ኢየሱስን የሚያምኑና የሚከተል ቀስ በቀስ እያደገ ወደ ብርሃን ይመራል። ነገር ግን ኢየሱስን የማያምንና የማይከተል ቀስ በቀስ በጨለማ ውስጥ ይወድቅና ውሎ አድሮ ወደ መንፈሳዊ ሞት ይመራል። የእኛ እምነት የእግዚአብሔርን ቃል በማስተዋልና በማወቅ ቀስ በቀስ ያድጋል?

**እንጸልይ፡– ጌታ ሆይ፣ እኛ ሰዎችን ሳንፈራ እምነታችንን ለሌሎች ሰዎች የንስሐ ስብከት እንድንሰብክ እርዳን፣ አሜን!**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

## 34. የንባብ ክፍል ዮሐንስ 9፥24–34 ወር፡ ቀን፡

### ርዕስ፡– እውነትን ሲናገር እነርሱ አይሰሙም

24. እነርሱ ዕውር የነበረውን ሰው ሁለተኛ ጠርተው፣ "አንተ እውነቱን በመናገር እግዚአብሔርን አክብር፣ ይህ ሰው ኃጢአተኛ መሆኑን እኛ እናውቃለን" አሉት።
25. ዕውር የነበረውም ሰው እንዲህ ሲል መለሰ፣ "እርሱ ኃጢአተኛ መሆኑን እኔ አላውቅም፣ ነገር ግን አንድ ነገር አውቃለሁ፣ ይኸውም እኔ ዕውር እንደ ነበርኩና አሁን ማየት እንደ ቻልኩ ብቻ ነው"
26. እነርሱም፣ "እርሱ ለአንተ ምን አደረገልህ? እንዴትስ ዓይኖችህ ከፈተ?" ብለው ጠየቁት።
27. እርሱም መልሶ እንዲህ አላቸው፣ "እኔ አስቀድሜ ነገርኋችሁ፣ ነገር ግን እናንተ መስማት አልፈለጋችሁም፣ ታዲያ፣ ለምን እንደገና መስማት ትፈልጋላችሁ? እናንተም የእርሱ ደቀ መዛሙርት መሆን ትፈልጋላችሁን?"
28. ከዚህ በኋላ እነርሱም እንዲህ እያሉ ሰደቡት፣ "አንተ የእርሱ ደቀ መዝሙር ነህ፣ ነገር ግን እኛ የሙሴ ደቀ መዛሙርት ነን፣ 29. እኛ እግዚአብሔር ሙሴን እንደ ተናገረው እናውቃለን፣ ነገር ግን ይህ ሰው ከየት እንደ ሆነ አናውቅም።" 30. ሰውየውም እንዲህ ሲል መለሰላቸው፣ "እናንተ ኢየሱስ ከየት እንደ መጣ አለማወቃችሁ፣ ነገር ግን እርሱ ዓይኖቼን ከፈተልኝ። 31. እኛ እግዚአብሔር ኃጢአተኞችን እንደማይሰማ እናውቃለን፣ ነገር ግን እግዚአብሔርን የሚያመልክና ፈቃዱንም የሚፈጽም ሰው ይሰማዋል።
32. ዕውር ሆኖ የተወለደውን ሰው ዓይኖች የከፈተ አለ ሲባል፣ ዓለም ከተፈጠረ ጀምሮ ማንም ሰምቶ አያውቅም።
33. ይህ ሰው ከእግዚአብሔር ባይሆን ኖሮ ምንም ይህን ለማድረግ ባልቻለም ነበር።"
34. እነርሱም እንዲህ ሲሉ መለሱለትና ከምኩራብ አወጡት፣ "አንተ ሁለንተናህ በኃጢአት ተወለድህ፣ አንተ እኛን ልታስተምር ነውን?"

ቁ. 31–33 እግዚአብሔር ራሱን የሚያከብሩትንና የሚታዘዙትን ሰዎች ጸሎት ይሠማል። ኢየሱስ የዕውሩን ዓይን የከፈተው እንደ እግዚአብሔር ፈቃድ ነው። ይህ በእርግጥ እግዚአብሔር የኢየሱስን ቃል እንደሚሰማ ምስክር ነው።

**ቁ**. 24,25 ***ፈሪሳውያን የኢየሱስን ሥራ አላወቁትም ነገር ግን ዕውሩ በራሱ ላይ የተደረገው ሥራ በኢየሱስ ኃይል መሆኑን አውቆ ንስሓን አገኘ። ዕውር ዓይኖቹ መከፈቱን በተአምራቱ በኩል አሁን መንፈሳዊ ዓይን ተከፍቶ አዲስ ተአምራትን ተለማመደ። እኛ በቃሉ በኩል ኢየሱስን በትክክል አይተናል?***

**ቁ**. 26,27 ***በቁጥር 15 ላይ የጠየቁትን ጥያቄ እንደገና በዚህ ቦታ መጠየቃቸው ግልጽ ነው። እግዚአብሔር ለፈሪሳውያን ምላሽ ሲሰጥ ግን አላስተዋሉም። እኛ ደግሞ እግዚአብሔር በብዙ ልዩ ልዩ መንገድ ምላሽ ሲሰጠን ነገር ግን አልሰማንምን? የጌታ ፈቃድና የእኛ ፈቃድ ልዩ ልዩ ስለሆነ የጌታን ፈቃድ አልተከተልንምን?***

**ቁ**. 34 ***ቀድሞ ዕውር የሆነው ሰው ኢየሱስ ከእግዚአብሔር ዘንድ እንደመጣ በንስሓ ለመመለስ ወዲያውኑ ከሕብረተሰቡ ጥሎ ወጣ። እርሱ እግዚአብሔር የሰጠውን ብርሃን ስላየ ሳይፈራ እውነትን ሰበከ። እኛ ደግሞ የወንጌልን እውነት ለመናገር ድፍረት እንዲሰጠን እንጸልያለን።***

***እንጸልይ፦ ጌታ ሆይ፤ በእግዚአብሔር ቃል በኩል ፈቃድህን ሰምተን እንድንታዘዝ እርዳን፤ አሜን!***

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

35. **የንባብ ክፍል** **ዮሐንስ** 9፥35−41 **ወር፡** **ቀን፡**

**ርዕስ፡− አንተ በሰው ልጅ ታምናለህ**?

35. **ኢየሱስም እርሱን ከምኵራብ እንዳስወጡት ሰማ፤ ባገኘውም ጊዜ፣ "አንተ በሰው ልጅ ታምናለህን**?" **አለው።**

36. **እርሱም እንዲህ ሲል ጠየቀው፣ "ጌታ ሆይ**! **እኔ በእርሱ አምናለሁ፣ እርሱ ማን ነው**?"

37. **ኢየሱስም፣ "አይተኸዋል፣ አሁንም ከአንተ ጋር የሚናገረው እርሱ ነው" አለው።**

38. **እርሱም፣ "ጌታ ሆይ**! **አምናለሁ" አለ፣ ሰገደለትም።**

39. **ኢየሱስም፣ "የማያዩ እንዲያዩ፣ የሚያዩም እንዲታወሩ፣ እኔ ወደዚህ ዓለም ለፍርድ መጥቻለሁ" አለ።**

40. **በዚያን ጊዜ በኢየሱስ አጠገብ የነበሩ ፈሪሳውያን አንዳንዶቹ ይህን ሰምተው እንዲህ አሉት፣ "ታዲያ፣ እኛም ዕውሮች መሆናችን ነው**?"**።**

41. **ኢየሱስም እንዲህ አላቸው፣ "እናንተ ዕውሮችስ ብትሆኑ ኃጢአት ባልሆነባችሁም ነበር፣ ነገር ግን እናንተ አሁን እናያለን ስለምትሉ፣ ኃጢአታችሁ ገና ይኖራል"**

**ቁ**. 35−41 **ኢየሱስ ለማያዩ ለሁሉም ሰዎች ዓይኖቻቸው እንዲያዩ አድርጐ የሚያዩ ሰዎች እንዲታወሩ አደረገ። ዕውር የሆነው ሰው ከኅብረተሰቡ ወጥቶ በጨለማ መካከል እያለ ነገር ግን የዓለም ብርሃን በሆነው በኢየሱስ ክርስቶስ በኩል እውነቱ ገባ።(ዮሐ፡** 9፥22,34) **ነገር ግን ፈሪሳዊያኖች ብዙ ነገሮች ስላላቸው ብዙ ዕቃዎችን ማየት ይችላሉ። ነገር ግን የዓለም ብርሃን የሆነውን ኢየሱስ ክርስቶስን አልተቀበሉም። ስለዚህ እነርሱ በጨለማና በጥፋት ውስጥ ለዘላለም ታስረው ይኖራሉ። የእኛ ዓይኖቻችን ተከፍቶ ብርሃን የሆነውን ኢየሱስን አይተን ፍቃዱን እያደረግን ነን**?

**ቁ**. 35 **ኢየሱስ ከአይሁዶች ዘንድ የወጣውን ዕውሩን ቸል ሳይል ወደ እርሱ ሄዶ ተገናኘ። ደግሞ ኢየሱስ ዛሬ እኛን ለመገናኘት ቸል ሳይል ወደ እኛ ይመጣል።**

**ቁ**. 39−41 **ኢየሱስ ዓለምን ሊፈርድ ወደ ዓለም መጣ። የእግዚአብሔር መንግስት የማዳን ዕቅድ መዳንና ፍርድን ሁለቱን ይዞ አለ። ኢየሱስ እንደ አይሁዶች ለማያምኑ ሰዎች ፍርድን ይሰጣል። ነገር ግን እንደ ዕውሩ ሰው ለሚያምኑ ሰዎች መዳንን ይሰጣል።**

**ቁ**. 35−38 **የተፈወሰው ዕውሩ ኢየሱስን በጥቂቱ እየተረዳ በመጨረሻ ለኢየሱስ ስግደትን አቀረበ። እኛ ደግሞ ኢየሱስን በጥልቀት ለማወቅ በእግሮቹ ፊት ወደሚስገድበት ቦታ ሄደናልን**?

**እንጸልይ፦ ጌታ ሆይ፤ እኛ ኢየሱስን ሳንቃወም እንደ ዕውሩ ሰው ተቀብለን እንድንኖር እርዳን**! **አሜን**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ**? **ማን ነው**?

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ** (**በስራ ላይ ማዋል**)

7. **ፀሎት**

36. **የንባብ ክፍል** **ዮሐንስ** 10፥1–6 **ወር፡** **ቀን፡**

**ርዕስ፡– መልካም እረኛን እንከተል**

1. **ኢየሱስ እንዲህ አለ፣ "እኔ በእውነት እላችኋለሁ፣ ወደ በጎች በረት በበሩ ሳይሆን በሌላ በኩል የሚገባ ሰው ሌባና ወንበዴ ነው።**

2. **ነገር ግን በበሩ የሚገባ እርሱ የበጎች እረኛ ነው፣**

3. **በር ጠባቂው በሩን ለእረኛ ይከፍትለታል፣ በጎቹም ድምፁን ይሰማሉ። እረኛም የራሱን በጎች በየስማቸው ይጠራቸዋል፣ እየመራም ወደ ውጭ ያወጣቸዋል።**

4. **የራሱን በጎች ሁሉ ካወጣ በኋላ ፊት ፊታቸው ይሄዳል፣ በጎቹም ድምፁን ስለሚያውቁ ይከተሉታል።**

5. **ነገር ግን በጎቹ የእንግዳ ድምፅ ስለማያውቁ ከእርሱ ይሸሻሉ እንጂ አይከተሉትም።"**

6. **ኢየሱስ ይህን ምሳሌ ነገራቸው፣ እነርሱ ግን ምን እንደ ነገራቸው አላስተዋሉም።"**

**ቁ.** 2–5 **ኢየሱስ እግዚአብሔር የላከው የእስራኤል ሕዝብ እውነተኛ እረኛ ነው። ኢየሱስ የእኛንም ስም ጠርቶ ከእኛ በፊት እየሄደ፣ በየቀኑ በለመለመው መስክ እያሰማራና ወደ እረፍት ውሃ ይመራናል።** (**መዝ፡** 23)

**ቁ.** 1–5 **በግ የእረኛውን ድምፅ ይሰማል። በኢየሱስ ውስጥ ያሉት ሰዎች ኢየሱስ ሲጠራ ለመመለስ እንደአምሳሉ ለተፈጠሩት ቀላል ነው። ነገር ግን ኢየሱስን የማያምኑ ሰዎች ኢየሱስ ሲጠራ ለመመለስ አይችሉም።**

**ቁ.** 3–5 **በግ የእረኛውን ድምፅ ሰምቶ ይከተላል። የሌላውን ድምፅ ሰምቶ አይከተልም። ዛሬ ለእኛ የሚያስፈልገን መንፈሳዊ እውቀት ነው። እውነትንና ውሸትን ለመለየት መንፈሳዊ ዓይን አለን**?

**ቁ.** 6 **ኢየሱስ የተናገረውን ሰዎቹ በደንብ አልተረዱም። እኛ በመንፈስ ቅዱስ አማካይነት ብቻ የኢየሱስ ድምፅ ማወቅ እንችላለን። ስለዚህ ቃሉን ስናነብብ መንፈስ ቅዱስ እንዲረዳን እንጸልያለን።**

**እንጸልይ፡- ጌታ ሆይ፣ ቃሉን ስናነብብ ቃሉን በደንብ አውቀን እንድንኖር እርዳን**! **አሜን።**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ**? **ማን ነው**?

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ** (**በስራ ላይ ማዋል**)

7. **ፀሎት**

37. **የንባብ ክፍል** **ዮሐንስ** 10፥7−21 **ወር፡** **ቀን፡**

**ርዕስ፦ እኔ መልካም እረኛ ነኝ**

7. **ስለዚህ ኢየሱስ እንደገና እንዲህ አላቸው፤ "እኔ በእውነት እላችኋለሁ፤ እኔ የበጎች በር ነኝ፤**

8. **ከእኔ በፊት የመጡት ሁሉ ሌቦችና ወንበዴዎች ናቸው፤ ነገር ግን በጎቹ የእነርሱን ቃል አልሰሙአቸውም።**

9. **በሩ እኔ ነኝ፤ ማንም በእኔ በኩል የሚገባ ሁሉ ይድናል፤ ይገባል፤ ይወጣልም፤ መሰማሪያም ያገኛል።**

10. **ሌባው ሊሰርቅ፣ ሊገድልና ሊያጠፋ ብቻ ይመጣል፤ እኔ የመጣሁት በጎቹ ሕይወት እንዲያገኙና የተትረፈረፈ ሕይወት እንዲኖራቸው ነው።**

11. "**መልካም እረኛ እኔ ነኝ፤ መልካም እረኛ ሕይወቱን ስለ በጎቹ አሳልፎ ይሰጣል።**

12. **ሞያተኛው እረኛ አይደለም፤ በጎቹ የእርሱ ስላልሆኑ፣ ተኵላ ሲመጣ በጎቹን ትቶ ይሸሻል፤ ተኵላውም በጎቹን ይነጥቃል፤ ይበትናቸዋል።**

13. **ምክንያትም የሚሸሸው ሞያተኛ ስለ ሆነና ለበጎቹ ደንታ ስለሌለው ነው።**

14. "**መልካም እረኛ እኔ ነኝ፤ እኔ በጎቼን አውቃለሁ፤ በጎቼም እኔን ያውቁኛል።**

15. **ይህም አብ እኔን እንደሚያውቀኝ እኔም አብን እንደማውቀው ነው። እኔ ስለ በጎቹ ሕይወቴን አሳልፌ እሰጣለሁ።**

16. **በዚህ መንጋ ውስጥ ያልሆኑ ሌሎች በጎች አሉኝ፤ እነርሱንም ማምጣት ይገባኛል፤ እነርሱ ድምፄን ይሰማሉ፤ አንድ እረኛው ታች አንድ መንጋም ይሆናሉ።**

17. **አባቴ እኔን ለወደደ ምክንያት እኔ እንደገና ሕይወቴን እወስዳት ዘንድ ሕይወቴን አሳልፌ ስለምሰጥ ነው።**

18. **ሕይወቴን በራሴ ፈቃድ አሳልፌ እሰጣለሁ እንጂ ከእኔ የሚወስዳት ማንም የለም፤ እኔ ሕይወቴን ለመስጠትና እንደገና ለመውሰድ ሥልጣን አለኝ፤ እኔ ይህን ትእዛዝ ከአባቴ ተቀበልሁ።**"

19. **የኢየሱስ ቃል የተነሣ በአይሁድ መካከል እንደገና መለያየት ሆነ።**

20. **ከእነርሱም ብዙዎቹ፣ "እርሱ ጋኔን ያደረበት እብድ ነው፤ ለምን ትሰሙታላችሁ?" አሉ።**

21. **ነገር ግን ሌሎች፣ "ይህ ጋኔን ያደረበት ሰው ንግግር አይደለም፤ ጋኔን የዕውርን ዓይን መክፈት ይችላልን?" አሉ።**

ቁ. 7−9 ኢየሱስ የበጐች በር ነው። ኢየሱስ ብቻውን ወደ እግዚአብሔር መንግሥት የሚያስገባ በርና መንገድ ነው። (ዮሐ፡ 14፥6) ስለዚህ እኛ ወደ እግዚአብሔር መንግሥት እንድንገባ የእግዚአብሔር ቤዛ በሕይወታችን ብንቀበልና በፍጹም ኢየሱስን ብናምን እንገባለን።

ቁ. 10 ኢየሱስ ለበጐች አዲስ ሕይወትና ብዙ ፀጋ የሚሰጥ ሰው ነው። አይሁዶች ሕዝቡን ለጥፋት ሲያደርጉ ኢየሱስ ግን ሕዝቡን ይባርካል።

ቁ. 16 ኢየሱስ በበጐች ጐረኖ ውጭ ያሉትን በጐችን ጠርቶ እረኛ ይሆናቸዋል። ገና በዙሪያችን ወደ ጐረኖ ያልገቡ ብዙ ሰዎች አሉ። ኢየሱስ በእኛ በኩል በጐረኖ ውስጥ ውጭ ያሉትን ወደ ጐረኖ እንድንጠራ ይፈልጋል። ዛሬ እኛ ደግሞ ከጐረኖ ውጭ ያሉትን ሰዎችን ወደ ኢየሱስ እንዲመጡ እንጋብዛቸዋለን።

ቁ. 19−21 ኢየሱስ በተናገረው ቃል ሕዝቡ ለሁለት ተለያዩ። የሚበዙ ሰዎች “ኢየሱስን ጋኔን ያደረበትና እብድ ነው” አሉ። ጥቂቶቹ “ጋኔን ያደረበት ሰው የዕውሩን አይኖች እንዴት ሊከፍት ይችላል” አሉ። እኛ ልናስብ የሚያስፈልገን ነገር ብዙ ጊዜ ባለማወቅ የብዙ ሰዎች ሀሳብ ትክክል ነው እያልን አንዳንድ ጊዜ ደግሞ የጥቂቶቹ ሀሳብ ትክክል አይደለም ብለን እናስባለን። በእኛ መካከል የእግዚአብሔር ፈቃድ ምንድን ነው? የጥቂቶቹን ሀሳብ ነው የእኛ ጆሮ የሚሰማው ወይስ የብዙዎችን?

እንጸልይ፡− ጌታ ሆይ፤ የእግዚአብሔርን ፈቃድ ምን እንደሆነ በሕይወታችን በደንብ ለይተን እንድናውቅ እርዳን! አሜን።

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

38. **የንባብ ክፍል** **ዮሐንስ** 10፥22–30 **ወር፡** **ቀን፡**

**ርዕስ፡– እኔና አባቴ አንድ ነን**

22. **በኢየሩሳሌምም የቤተ መቅደስ መታደስ በዓል ሆነ፤ ጊዜውም ክረምት ነበረ፤**
23. **ኢየሱስ በቤተ መቅደስ ግቢ፣ በሰሎሞን መመላለሻ ያልፍ ነበር፤**
24. **በዚያን ጊዜ አይሁድ ኢየሱስ በዙሪያው ተሰብስበው፣ "እስከ መቼ ልባችንን በጥርጣሬ ታቈየናለህ? አንተ ክርስቶስ ከሆንህ በግልጽ ንገረን" አሉት።** 25. **ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰላቸው፤ "እኔ ነግሬአችሁ ነበር፤ ነገር ግን እናንተ አታምኑም፤ እኔ በአባቴ ስም የምሠራው ሥራ ስለ እኔ ይመሰክራል።**
26. **ነገር ግን እናንተ ከበጎቼ መንጋ ስላልሆናችሁ አታምኑም።**
27. **በጎቼ ድምፄን ይሰማሉ፤ እኔ ጎቼን አውቃቸዋለሁ፤ እነርሱም ይከተሉኛል፤**
28. **እኔ ለእነርሱ የዘላለም ሕይወት እሰጣቸዋለሁ፤ ስለዚህ እነርሱ ከቶ አይጠፉም፤ ከእኔ እጅ ሊነጥቃቸው የሚችል ማንም የለም።**
29. **እነርሱን ለእኔ የሰጠኝ አባቴ ከሁሉ ይበልጣል፤ ከአባቴም እጅ እነርሱን ማንም ሊነጥቃቸው አይችልም።**
30. **እኔና አብ አንድ ነን።"**

**ቁ.** 27–28 **ኢየሱስ የራሱን በጐች ጠርቶ ተናገራቸው። ኢየሱስ የዘላለምም ሕይወትና የመዳን ዋስትና ሰጣቸው። እናንተ ስለ ደህንነታችሁ እርግጠኛ አይደላችሁም? እኛ በጌታ ውስጥ ስለምንኖር እኛን ከኢየሱስ እጅ የሚነጥቅ ማንም የለም።** (**ሮሜ፡** 8፥35–39)

**ቁ.** 29–30 **ኢየሱስ ከአባቱ ጋር አንድ የሆነ ሰው ነው። ኢየሱስ ከአባቱ ከእግዚአብሔር ጋር እኩል ነው። የእግዚአብሔር ልጅ ኢየሱስ ከአባቱ ሥልጣኑንና ኃይሉን ተቀበለ። ስለዚህ የራሱን ሰዎች በብርቱ ይጠብቃል። ይህ አንዳንድ የዓለም ሥልጣንና ኃይል ከኢየሱስ ስልጣን ሊበልጥ አይችልም። እነዚህ ወራቶች ለምን ዓይነት ችግሮች እርግጠኛ ሳትሆኑ ተጨንቃችኃል? በኢየሱስ ሥልጣን እጅ ውስጥ ያለን እኛ በጥንቃቂ እንደሚጠበቅ ስዕል ስለን ልናስብ ያስፈልጋል።**

**ቁ.** 24–27 **በጐቹ የእረኛውን ድምፅ ሰምተው ወዳውኑ ይከተላሉ። አይሁዶች የኢየሱስን ድምፅ አይሰሙም። ምክንያቱም አይሁዶች የኢየሱስ በጐች**

**አይደሉም። እኛ የኢየሱስን ድምፅ ሰምተን ምላሽ ሰጠን? ዛሬ በጐቹ የሆኑት የእረኛውን ድምፅ በደንብ ሰምተው ኢየሱስን ይከተላሉ።**

**እንጸልይ፦ ጌታ ሆይ፤ የእግዚአብሔርን ቃል አንብበን የኢየሱስን ድምፅ በደንብ አውቀን እንደ ቃሉ እንድንኖር እርዳን አሜን!**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

39. **የንባብ ክፍል** **ዮሐንስ** 10፥31–42 **ወር፡** **ቀን፡**

**ርዕስ፡– ለምን እኔን በስድብ ከሰሱ?**

31. **በዚህ ጊዜ አይሁድ ኢየሱስን ሊወግሩት እንደገና ድንጋይ አነሡ።**

32. **ነገር ግን ኢየሱስም፣ "ከአብ የሆኑ ብዙ መልካም ሥራዎችን አሳየኋችሁ፣ ታዲያ፣ እናንተ ከእነዚህ ስለ የትኛው ለእኔ ትወግሩኛላችሁ?" አላቸው።** 33. **እነርሱም፣ "እኛ አንተን በድንጋይ የምንወግርህ ስለ መልካም ሥራህ አይደለም፤ በእግዚአብሔር ላይ የስድብ ቃል ስለ መናገርህ ነው እንጂ፤ አንተም ሰው ስትሆን ራስህን አምላክ ስላደረግህ ነው" ብለው መለሱለት።** 34. **ኢየሱስም እንዲህ አላቸው፣ "በሕጋችሁስ 'እናንተ አማልክት ናችሁ አልሁ' የሚል ተጽፎ የለምን?** 35. **የእግዚአብሔር ቃል የመጣላቸውን ቅዱስ መጽሐፍ 'አማልክት' ብሎ ካላቸው፣ እንግዲህ ቅዱስ መጽሐፍን ሊሻር አይቻልም፣** 36. **ታዲያ፣ አብ የቀደሰውንና ወደ ዓለም የላከውን 'የእግዚአብሔር ልጅ ነኝ' ስለ አለ ስለምን 'በእግዚአብሔር ላይ የስድብ ቃል ትናገራለህ' ትሉታላችሁ?**

37. **እኔ የአባቴን ሥራ ባላደርግ አትመኑኝ፣**

38. **ነገር ግን እኔ የአባቴን ሥራ የማልሠራ ከሆንኩ እናንተ እኔን ባታምኑኝ እንኳ፣ በሥራዬ እመኑ፣ በዚህ ዓይነት እናንተ አብ በእኔ እንደ ሆነና እኔም በአብ እንደ ሆንኩ በሚገባ ታውቃላችሁ።"**

39. **አይሁድ እንደገና ኢየሱስን ሊይዙት ሞከሩ፣ ነገር ግን ኢየሱስ ከእጃቸው አመለጠ።**

40. **ኢየሱስ ዮሐንስ መጀመሪያ ያጠምቅበት ወደ ነበረው ስፍራ ወደ ዮርዳኖስ ማዶ ተመለሰ፣ እንደገናም በዚያም ሰነበተ፣**

41. **ብዙ ሰዎችም ወደ ኢየሱስ መጡ። እነርሱም፣ "ዮሐንስ ምንም ተአምር አላደረገም፣ ነገር ግን ዮሐንስ ስለዚህ ሰው የተናገረው ሁሉ እውነት ነበረ" አሉ።** 42. **በዚያም ሰፍራ ብዙዎች በኢየሱስ አመኑ።**

**ቁ**. 34–36 **መዝ፡** 82፥6**ን ጠቅሶ ኢየሱስ ራሱ የእግዚአብሔር ልጅ እንደ ሆነ አስረዳ።**

**ቁ**. 39 **ኢየሱስ በመስቀል ላይ የሚሰቀልበት ጊዜ ገና ስላልደረሰ ከዚያ ቦታ ወጣ። ኢየሱስ ሁል ጊዜ የእግዚአብሔርን ጊዜ አይቶ ፈቃዱን ተከትሎ ከቦታ**

ወደ ቦታ ይንቀሳቀሳል። እኛ እንደ ኢየሱስ የእግዚአብሔርን ፈቃድ አውቀን ለማድረግ እንኖራለን?

**ቁ.** 31−33 አይሁዶች ኢየሱስን "እግዚአብሔርን ሰድበዋል" ብለው በዚህ ምክንያት በድንጋይ ወግረው ለመግደል ሞከሩ። (ዘለዋ፡ 24፥16) አይሁዶች የእግዚአብሔርን ቃል አንብቦ እንደ ቃሉ አደረጉ። ነገር ግን ዛሬ እኛ ለጠባብ አእምሮ ልንጠነቀቅ ይገባል።

**እንጸልይ፡**− ጌታ ሆይ፤ እኛ ሁል ጊዜ ለቃሉ ታዝዘን በሕይወት እንድንኖር እርዳን፤ አሜን!

1. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ

2. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት

3. እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?

4. የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና

5. ትምህርት

6. ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)

7. ፀሎት

40. **የንባብ ክፍል** **ዮሐንስ** 11፥1–16 **ወር፡** **ቀን፡**

**ርዕስ፡– ስለ እግዚአብሔር ክብር**

1. **በማርያምና በእኅቷ በማርታ መንደር በቢታንያ ይኖር የነበረው አልዓዛር ታሞ ነበር።**

2. **ይህች ማርያም የኢየሱስን እግር ሽቶ የቀባችውና በጠጉርዋ ያበሰችው ናት፣ የታመመውም አልዓዛር የእርስዋ ወንድም ነበር።**

3. **እኅትማማቾቹም፣ "ጌታ ሆይ፣ ያ የምትወደው ሰው ታሞአል" ብለው ወደ ኢየሱስ ላኩበት።**

4. **ኢየሱስም ይህን በሰማ ጊዜ፣ "ይህ ሕመም ለሞት የሚያደርስ አይደለም፣ ነገር ግን ለእግዚአብሔር ክብር እንዲሆንና የእግዚአብሔርን ልጅም በዚህ ምክንያት እንዲከበር ነው" አለ።**

5. **ኢየሱስ ማርታንና እኅትዋን ማርያም ወንድማቸውን አልዓዛርንም ይወድ ነበር።**

6. **ሆኖም አልዓዛር መታመሙን በሰማ ጊዜ በነበረበት ስፍራ ሁለት ቀን ቈየ።**

7. **ከዚህ በኋላ ደቀ መዛሙርቱን፣ "ወደ ይሁዳ ምድር እንደገና እንሂድ" አላቸው።**

8. **ደቀ መዛሙርቱም፣ "መምህር ሆይ! አይሁድ ከጥቂት ጊዜ በፊት ሊወግሩህ ይፈልጉ ነበር፣ ታዲያ እንደገና ወደዚያ ተመልሰህ ትሄዳለህን?" አሉት።**

9. **ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰላቸው፣ "በቀን ውስጥ ያለው ጊዜ አሥራ ሁለት ሰዓት አይደለምን? በቀን የሚመላለስ የዚህን ዓለም ብርሃን ስለሚያይ አይሰናከልም።**

10. **ነገር ግን በሌሊት የሚመላለስ ብርሃን ስለሌለው ይሰናከላል።"**

11. **ይህን ከነገራቸው በኋላ፣ "ወዳጃችን አልዓዛር ተኝቶአል፣ እኔም ግን ከእንቅልፉ ላስነሣው እሄዳለሁ" አላቸው።**

12. **ደቀ መዛሙርቱም፣ "ጌታ ሆይ፣ አልዓዛር ተኝቶ ከሆነ ይድናል" አሉት።**

13. **ኢየሱስ ይህን የተናገረው ስለ አልዓዛር መሞት ነበር፣ ነገር ግን ደቀ መዛሙርቱ ስለ እንቅልፍ የተናገረ መስሎአቸው ነበር።**

14. **ስለዚህ ኢየሱስ በግልጥ እንዲህ አላቸው፣ "አልዓዛር ሞቶአል፣**

15. **ስለ እናንተ በዚያ ባለመኖሬ ደስ ይለኛል፣ ስለ ይህ ሥራ እናንተ ታምናላችሁን፣ ነገር ግን አሁን ወደ አልዓዛር እንሂድ።"**

16. **ከዚያም ዲዲሞስ የተባለው ቶማስ ሌሎቹን ደቀ መዛሙርት፣ "እኛም ከኢየሱስ ጋር እንድንሞት እንሂድ" አላቸው።**

**ቁ**. 6,7 ኢየሱስ በሽተኛ የሆነው ሰው እንደ ሞተ ሲሰማ ወዲያውኑ አልሄደም። ምክንያቱም አሁን ለእግዚአብሔር ጥሩ ጊዜ ስላልሆነ ነው። ስለዚህ እኛ የጸሎታችን መልስ ወዲያውኑ ባይመጣ ነገረ ግን እግዚአብሔርን በእምነት እንጠባበቃለን።

**ቁ**. 8–10 ኢየሱስ በእግዚአብሔር ብርሃን ስለመጣ እኛ በብርሃን መካከል በጥንቃቄ እንድንሄድ አድርጓል። ደቀ መዛሙርቱ ወደ ይሁዳ ሀገር ለመሄድ ፈሩ። ግን ኢየሱስ ራሱ ከእነርሱ ጋር እንደሚሄድ በጥንቃቄ ተናገረ። ለእኛ በጣም አደጋ የሆነው ይህ ዓለም አይደለም። አደጋው ብርሃን ከሆነው ከኢየሱስ ጋር አለመሄዱ ነው። ዛሬ ብርሃን ከሆነው ከኢየሱስ ጋር ብንሄድ በምንም ነገር አንወድቅም።

**ቁ**. 12–15 ኢየሱስ በዓልአዛር በተደረገ ሁኔታ በኩል ደቀ መዛሙርቱ እምነትን እንደጨመሩ አይቶ ተደስተ። ደግሞ ኢየሱስ እንደ ደቀ መዛሙርቱ በእኛ ሕይወት እምነታችን ሲያድግ አይቶ ሊደሰት ይፈልጋል።

**ቁ**. 1–5 የሚያምኑ ሰዎች ደግሞ በችግር ውስጥ ሊኖሩ ይችላሉ። የዓላአዛር፣ የማርያምና የማርታ ቤት ለኢየሱስ የዕረፍት ቦታ ነበር። ይህ ቤተሰብ ኢየሱስ የሚወዳቸው ቤተሰብ ነው። ነገር ግን ይህ ቤተሰብ ጥልቅ አዘን ደርሶባቸዋል። ደግሞም በሕይወታችን ድንገተኛ ችግር ደርሶብናልን? በእምነት ይህን ዓይነት ሁናቴ በመመልከት እናሸንፋለን።

**እንጸልይ፦** ጌታ ሆይ፤ በማናቸውም ችግር ሁል ጊዜ የጌታን ሥራ በመጠበቅ በእምነት እንድንታገስ እርዳን፤ አሜን!

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

41. **የንባብ ክፍል** **ዮሐንስ** 11፥17-27 **ወር፡** **ቀን፡**

**ርዕስ፡- ኢየሱስ ትንሣኤና ሕይወት ነው**

17. **ኢየሱስ እዚያ በደረሰ ጊዜ አልዓዛር ከተቀበረ አራት ቀን ሆኖት አገኘው።**

18. **ቢታንያ ከኢየሩሳሌም የምትርቀው ሦስት ኪሎ ሜትር ያህል ነው።**

19. **ብዙዎች አይሁድም ማርታንና ማርያምን ስለ ወንድማቸው ሞት ለማጽናናት ወደ እነርሱ መጥተው ነበር።**

20. **ማርታ የኢየሱስን መምጣት በሰማች ጊዜ ልትቀበለው ወጣች፤ ነገር ግን ማርያም በቤት ቀርታ ነበር።**

21. **ማርታም ኢየሱስን እንዲህ አለችው፤ "ጌታ ሆይ፤ አንተ በዚህ ብትሆን ኖሮ፤ ወንድሜ ባልሞተ ነበር።**

22. **አሁንም ቢሆን የምትለምነውን ሁሉ እግዚአብሔር እንደሚሰጥህ አውቃለሁ።"**

23. **ኢየሱስም፤ "ወንድምሽ እንደገና ከሞት ይነሣል" አላት።**

24. **ማርታም፤ "በመጨረሻው ቀን በትንሣኤ ጊዜ ከሞት እንደሚነሣ አውቃለሁ" አለችው።**

25. **ኢየሱስም እንዲህ አላት፤ "እኔ ትንሣኤና ሕይወት ነኝ፤ በእኔ የሚያምን ቢሞት እንኳ በሕይወት ይኖራል፤**

26. **በሕይወት የሚኖርና በእኔም የሚያምን ሁሉ ከቶ አይሞትም፤ ይህን ታምኚለሽ?" አላት።**

27. **ማርታም፤ "አዎ ጌታ ሆይ! አንተ ወደ ዓለም የሚመጣው ክርስቶስ የእግዚአብሔር ልጅ መሆንህን አምናለሁ" አለችው።**

**ቁ**. 21-23 **ኢየሱስ ለማርታ የትንሣኤን ተስፋ ሰጣት። ኢየሱስ የማርታን ተስፋ ቸል አለማለት አይቶ ዓልአዛርን ከሞት እንደሚነሣ ተናገረ። ኢየሱስ የእኛ ችግሮቻችንን አውቆ ከእኛ ተስፋ የሚበልጥ መልስ ይመልሳል።**

**ቁ**. 25,26 **ኢየሱስ ትንሣኤና ሕይወት ነው። ስለዚህ ኢየሱስን የሚያምኑ ሰዎች ደግሞ የዘላለም ሕይወት አላቸው። ይህ የእኛ ሥጋችን ቢሞት በኢየሱስ ትንሣኤ በኩል ለዘላለም እንኖራለን። እኛ በኢየሱስ ክርስቶስ በኩል የዘላለም ሕይወት አለን። በሕይወታችን በየቀኑ መስቀላችንን ተሸክመን ጌታን ስንከተል የክብር ትንሣኤና የዘላለም ሕይወት በእርግጥ እንወስዳለን።**

**ቁ**. 17 **ኢየሱስ ከመምጣቱ በፊት ዓልአዛር ሞቶ ነበረ። እርሱም ከሞተ አራተኛ ቀን ሆኖታል። ምንም ተስፋ ያለው አይደለም። ነገር ግን ጌታ በጥልቅ ጨለማ ውስጥ መሥራቱን እናምናለን።**

**ቁ**. 21,24 **ማርታ ከሰዓትና ከቦታ አልፎ የሚሰራውን የኢየሱስን ችሎታ አላመነችም። ደግሞም የዓልአዛር ትንሣኤ አሁኑኑ እንደሚሆን አልተቀበለችም። ወደ ፊት ያለውን ትንሣኤ ተረዳችው። እኛ ደግሞ እንደ ማርታ የኢየሱስን ሥልጣን አልተረዳንም**?

**እንጸልይ፦ ጌታ ሆይ፤ እኛ በየቀኑ መስቀላችንን ተሸክመን ኢየሱስን እየተከተልን እንድንኖር እርዳን፤ አሜን**!

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ**? **ማን ነው**?

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ** (**በስራ ላይ ማዋል**)

7. **ፀሎት**

42. **የንባብ ክፍል** **ዮሐንስ** 11፥28−44 **ወር፡** **ቀን፡**

**ርዕስ፦ ኢየሱስ እንባውን አፈሰሰ**

28. ማርታ ይህን ከተናገረች በኋላ ሄደችና እኅትዋን ማርያምን በስውር ጠርታ፣ “መምህር መጥቶአል፣ አንቺንም ይጠራሻል” ብላ አለቻት።

29. ማርያም ይህን በሰማች ጊዜ ፈጥና ተነሥታ ወደ ኢየሱስ ሄደች።

30. በዚህ ጊዜ ኢየሱስ፣ ማርታ እርሱን በተቀበለችበት ስፍራ ነበር እንጂ፣ ገና ወደ መንደር አልገባም ነበር።

31. ማርያምን ሲያጽናኑ በቤት ውስጥ የነበሩ አይሁድም፣ ማርያም ፈጥና ተነሥታ ስትወጣ አይተው፣ ወደ አልዓዛር መቃብር ሄዳ የምታለቅስ መስሎአቸው ተከተሉአት።

32. ማርያምም ኢየሱስ ወደ ነበረበት ቦታ መጥታ ባየችው ጊዜ እግሩ ላይ ወደቀችና “ጌታ ሆይ፣ አንተ እዚህ ብትሆን ኖሮ፣ ወንድሜ ባልሞተ ነበር” አለችው።

33. ኢየሱስ ማርያምን ስታለቅስና አብረዋት የመጡትም አይሁድ ሲያለቅሱ ባየ ጊዜ በመንፈሱ እጅግ አዝኖ ታወከ፣

34. ኢየሱስ፣ “አልዓዛርን የት ነው የቀበራችሁት?” አለ። እነርሱም “ጌታ ሆይ! መጥተህ እይ!” አሉት።

35. ኢየሱስም እንባውን አፈሰሰ።

36. ስለዚህ አይሁድ፣ “ኢየሱስ አልዓዛርን እንዴት ይወደው እንደ ነበረ አያችሁ!” አሉ።

37. ነገር ግን ከእነርሱ አንዳንዶቹ፣ “የዕውርን ዓይኖች የከፈተ፣ ይህ ሰው እንዳይሞት ማድረግ አይችልም ነበር?” አሉ።

38. ኢየሱስ ልቡ በጣም እያዘነ ወደ መቃብሩ ሄደ፣ መቃብሩ በድንጋይ የተዘጋ ዋሻ ነበር።

39. ኢየሱስ “ድንጋዩን አንሡት!” አለ። የሟቹ እኅት ማርታ፣ “ጌታ ሆይ፣ ከሞተ አራት ቀን ሆኖታል፣ አሁን ይሸታል” አለችው።

40. ኢየሱስም፣ “በታምኚስ የእግዚአብሔርን ክብር ታያለሽ ብዬ አልነገርሁሽም?” አላት።

41. ስለዚህ ሰዎቹ ድንጋዩን አነሡት፣ ከዚህ በኋላ ኢየሱስ ወደ ላይ ተመልክቶ እንዲህ አለ፣ “አባት ሆይ! ስለ ሰማኸኝ አመሰግንሃለሁ፣

42. ሁልጊዜም እንደምትሰማኝ አውቃለሁ፣ ነገር ግን ይህን መናገሬ በዚህ የቆሙ ሰዎች፣ አባት እንደ ላክኸኝ ያምኑ ዘንድ ነው።”
43. ኢየሱስ ይህን ከተናገረ በኋላ፣ “አልዓዛር! ና ውጣ!” ብሎ በታላቅ ድምፅ ተናገረ።
44. የሞተውም አልዓዛርም እጆቹና እግሮቹ በመገነዣ እንደ ተገነዙ ከመቃብሩ ወጣ፣ ፊቱም በጨርቅ እንደ ተጠመጠመ ነበር፣ ኢየሱስም “መግነዙን ፍቱትና ተዉት ይሂድ!” አላቸው።

ቁ. 28-30 ኢየሱስ ማርያምንና ማርታን ጠርቶ እንዲገናኙ ፈለገ። ዛሬ ደግሞ ኢየሱስ ወደ እኛ መጥቶ የእኛን ስም ይጠራል። በየቀኑ እየመጣ ልባችንን እያንኳኳ የጌታን ድምፅ ያሰማል።

ቁ. 33-35 ኢየሱስ ዓልአዛር ስለሞተ የሚያለቅሱ ሰዎችን አይቶ እንባውን አፈሰሰ። የጌታ እንባ ማፍሰስ ማለት፡- 1ኛ/ በኃጢአት ምክንያት የሚሞቱትን ሰዎችን አይቶ ወድዶ ማልቀሱን 2ኛ/ ለሰዎች ኃጢአት የሚከፈል የኃጢአት ይቅርታና የራሱ የወደፊት ሞት አይቶ በኃጢአት መካከል የሚሞቱ ሰዎችን መውደዱን ይገልፃል።

ቁ. 39,40 ኢየሱስ የእግዚአብሔርን ክብር ለማሳየት ከዓልአዛር መቃብር ድንጋዩን አንሱ ብሎ አዘዘ። ኢየሱስ የጨለማ የሞት ዋሻ ከፈተ። ይህ ማለት ለሞተው ሰው ነፍስ አዲስ ሕይወት ሰጠ ማለት ነው። ደግሞ እኛ በሕይወታችን እንደ ዓልአዛር መቃብር ተስፋ ቆረጥን? የትንሣኤው ኢየሱስ ያንን ድንጋይ አንሱ ያለውን ድምጹን ብንሰማ በእርግጥ የእግዚአብሔርን ክብር ማየት ይሆንልናል።

እንጸልይ፡- ጌታ ሆይ፤ እኛን ከጨለማ ሥልጣን አውጥተህ የእግዚአብሔር ልጆች እንድንሆን ስለፈቀድክ እናመሰግናለን፤ አሜን።

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

43. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 11፥45−57 **ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፡− ኢየሱስን ለመግደል ሤራ መጀመር**

45. ***ማርያምን ለማጽናናት መጥተው ከነበሩት አይሁድ ብዙዎቹ፣ ኢየሱሰ ያደረገውን አይተው በኢየሱስ አመኑ።***

46. ***ነገር ግን ከእነርሱ አንዳንዶቹ ወደ ፈሪሳውያን ሄደው ኢየሱስ ያደረገውን ነገሩአቸው።***

47. ***ስለዚህ የካህናት አለቆችና ፈሪሳውያን የሸንጎውን አባሎች ሰብስበው እንዲህ አሉ፤ “ይህ ሰው ብዙ ተአምራት ስለሚያደርግ ምን ብናደርግ ይሻላል?***

48. ***እንዲሁ ብንተወው ሰው ሁሉ በእርሱ ያምናል፣ ሮማውያንም መጥተው ቤተ መቅደሳችንንና ሕዝባችንን ሁሉ ይደመስሳሉ።”***

49. ***ከእነርሱ አንዱ በዚያን ዓመት የካህናት አለቃ የነበረው ቀያፋ እንዲህ አለ፣ “እናንተ ምንም አታውቁም፣***

50. ***ሕዝብ ሁሉ ከሚጠፋ አንድ ሰው ስለ ሕዝብ ቢሞት ለእናንተ የሚሻላችሁ መሆኑን አታስተውሉም።”***

51. ***ቀያፋም ይህን የተናገረው፣ ከራሱ አልነበረም፣ ነገር ግን በዚያን ዓመት እርሱ የካህናት አለቃ ስለ ነበረ፣ ኢየሱስ ለአይሁድ ሕዝብ እንደሚሞት ትንቢት መናገሩ ነበር፣***

52. ***ቀያፋ የሚሞተው ስለ ሕዝቡ ብቻ ሳይሆን፣ የተበተኑትንም የእግዚአብሔርን ልጆች በአንድነት ለመሰብሰብ ነው።***

53. ***ስለዚህ ከዚያ ቀን ጀምሮ እነርሱ ኢየሱስን ለመግደል ተማከሩ።***

54. ***ስለዚህ ኢየሱስ ከዚያ ወዲያ በአይሁድ መካከል በግልጥ አልተመላለሰም፣ ነገር ግን ኢየሱስ ከዚያ ወጥቶ በምድረ በዳ አጠገብ ወዳለችው ኤፍሬም ወደምትባለው ከተማ ሄደ፣ በዚያም ከደቀ መዛሙርቱ ጋር ሰነበተ።***

55. ***የአይሁድ የፋሲካ በዓል ቀርቦ ነበር፣ ብዙዎቹም የፋሲካ በዓል ከመድረሱ በፊት፣ ራሳቸውን ለማንጻት ከአገር ቤት ወደ ኢየሩሳሌም ወጡ፣***

56. ***እነርሱም ኢየሱስን ይፈልጉት ነበር፣ በቤቱ መቅደስም ቆመው፣ “ምን ይመስላችኋል? ለበዓሉ አይመጣ ይሆን?” ተባባሉ።***

57. ***የካህናት አለቆችና ፈሪሳውያን ኢየሱስን ይይዙት ዘንድ ኢየሱስ የት እንዳለ የሚያውቅ ሰው እንዲጠቍም ትእዛዝ ሰጥተው ነበር።***

**ቁ**. 53,54 ኢየሱስን ለመግደል አይሁዶች በፍጥነት ያደረጉትን አይተናል። ኢየሱስ የእግዚአብሔርን ጊዜ እየጠበቀ ቀሰ በቀስ ያደረገውን ተመልክተናል። ኢየሱስ ራሱን ለመግደል የሚፈልጉትን አይሁዶችን አውቆ ከደቀ መዛሙርቱ ጋር ሕብረትን አደረገ። ኢየሱስ ብቻውን የእግዚአብሔር ተልዕኮውን ይዞ መኖሩን ከሕይወቱ ቤዛ የሆነበትን ትምህርት አግኝተናል።

**ቁ**. 45,46 ብዙ አይሁዶች ከሞት የተነሣውን ዓልአዛርን ካዩት በኋላ ኢየሱስን ማመን ጀመሩ። ነገር ግን አንዳንዶቹ ወደ ፈሪሳዊያን ሄደው ኢየሱስ ያደረገውን ሁሉ ነገሩ። አሁን ወንጌልን ሰምተው በሚታዘዙት ሰዎች በኩል የእግዚአብሔር መንግሥት እየሠራ ይገነባል። ነገር ግን ሌሎች አንዳንዶቹ በጨለማ ቤተ ክርስቲያንንና የማያምኑትን ለመፈተን ይሞክራሉ። እኛ በየትኛው ላይ ቆመናል? እኛ ሁልጊዜ በእግዚአብሔር ጐን ላይ ቆመን የእግዚአብሔርን መንግሥት ሥራ አብረን እንድንሰራ ልንጸልይ ያስፈልጋል።

**ቁ**. 47,53,56,57 አይሁዶች ከዓልአዛር መነሣት በኋላ የሁከት ጊዜ አግኝተው ኢየሱስን ለመግደል ወሰኑ። ምክንያቱም የኢየሱስን ሥልጣንና ኃይል ለራሳቸው ለመውሰድ ያሰቡት ሀሳብ ነው።

**እንጸልይ፦** ጌታ ሆይ፤ እኛ ምቾትንም ቢሆን ችግሮችንም ስለ ጌታ መንግሥት በደስታ እንድንቀበል እርዳን፤ አሜን!

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

44. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 12፥1−11 **ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፡− የኢየሱስን ሞት አዘጋጁ**

1. **የአይሁድ የፋሲካ በዓል ስድስት ቀን ሲቀረው፥ ኢየሱስ ከሞት ያስነሣው አልዓዛር ወደሚኖርበት፣ ወደ ቢታንያ መጣ።** 2. **በዚያ እነርሱ ለኢየሱስ ራት አዘጋጁለት፣ ማርታ ታገለግል ነበር፣ አልዓዛርም ከኢየሱስ ጋር በማዕድ ከተቀመጡት አንዱ ነበር።** 3. **በዚያን ጊዜ ማርያም ዋጋው ውድ የሆነ፣ ግማሽ ሊትር ንጹሕ የናርዶስ ሽቱ አምጥታ በኢየሱስ እግር ላይ ቀባች፣ እግሩንም በጠጕሯ አበሰች፤ ቤቱንም የሽቱው መዓዛ ሞላው።** 4. **ከደቀ መዛሙርቱ አንዱ ኢየሱስን አሳልፎ የሚሰጠው አስቆሮታዊው ይሁዳ እንዲህ አለ፣** 5. "**ይህ ሽቱ በሦስት መቶ ዲናር ተሸጦ ገንዘቡ ለድሆች ለምን አልተሰጠም**?" 6. **አስቆሮታዊው ይሁዳ ይህን የተናገረው፥ ለድሆች አዝኖ ሳይሆን፣ እርሱ ሌባ ስለ ነበረ ነው፥ የገንዘብ ከረጢት የሚይዝ እርሱ በመሆኑ በከረጢቱ ለራሱ የሚጠቀም ሌባ ስለ ነበር።**

7. **ኢየሱስም እንዲህ አለ፣** "**ማርያም ያደረገችው ተዉአት፤ እርስዋ ይህ ሽቱን ለምቀበርበት ቀን ዝግጅት ስለ ሆነ።**

8. **ድሆች ሁልጊዜ ከእናንተ ጋር ናቸው፥ እኔ ግን ሁልጊዜ ከእናንተ ጋር አልሆንም።**

9. **በዚያን ጊዜ ብዙ አይሁድ ኢየሱስ በዚያ በቢታንያ መሆኑን አውቀው መጡ፣ የመጡትም ስለ ኢየሱስ ብቻ ሳይሆን ኢየሱስ ከሞት ያስነሣውን አልዓዛርንም ለማየት ነበር።**

10. **ስለዚህ የካህናት አለቆች አልዓዛርን ጭምር ለመግደል ተማከሩ፣**

11. **ይህም በአልዓዛር ምክንያት ብዙ አይሁድ ወደ ኢየሱስ እየሄዱ ያምኑ ስለ ነበር ነው።**

**ቁ.** 1−3 **ከሞት የተነሣው የዓልአዛር ቤተሰብ ኢየሱስን ወደ ቤታቸው ጋብዘው ሐሴት አደረጉ። ዓልአዛርም ከኢየሱስ ጋር ኅብረት በማድረጉ ተደሰተ። ማርታ ትጉ አገልጋይ ነበረች። ማርያምም በውድ ዋጋ የተገዛውን ሽቶ ወስዳ የኢየሱስን እግር ቀባች።**

**ቁ.** 4−7 **የአስቆሮንቱ ይሁዳ ስለ ድሆች አዝኖ ተመለከተ። ነገር ግን በእርሱ ውስጥ ቅራኔ ነበረበት። ይሁዳ ገንዘብን ፈልጐ ኢየሱስን የሸጠ ሰው ነው። እኛ ስለገንዘብ ቅራኔ ለእግዚአብሔር መንግሥት የምንሰጠውን ገንዘብ ተፀፀትንህ?**

ለምሳሌ ያህል፡- በአንድ ምንጭ ያለውን ውሃ ሁል ጊዜ ከጠጣን ጥሩ ውሃ ማግኘት ይቻላል። ነገር ግን ያንን ምንጭ ሁልጊዜ ካልጠጣን ጥሩ ውሃ ማግኘት አይቻልም። ውሃው ሁልጊዜ ስለማይቀዳ በምንጩ ውስጥ ያለው ቆሻሻ ውሃ ይሆናል። ስለዚህ እንደ ምሳሌው እኛ በእግዚአብሔር ቤት ያለን ወጣቶች፣ ሽማግሌዎች፣ ሴቶች፣ መጋቢያን፣ ወዘተ ከገንዘባችን ለእግዚአብሔር መንግሥት ሥራ እንድንሰጥና ደሆችንም እንድንረዳ እግዚአብሔር ይፈልጋል። ይህንን ስናደርግ እግዚአብሔር በረከቱን ለእኛ ይሰጠናል።

**ቁ**. 8 ለኢየሱስ ውድ ዋጋ ያለውን ስጦታ የሰጡት ሰዎች ለተራቡ ሰዎች የራሳቸውን ዕቃዎችንም ይሰጣሉ። ምክንያቱም እነርሱ ጌታንና ጐረቤትን ስለሚወዱ ነው።

**ቁ** 9-11 ከዓልአዛር ትንሣኤ በኋላ ብዙ ሰዎች ኢየሱስን አመኑ። በእኛ አማካይነት ኢየሱስን ያመኑ ሰዎች ስንት ናቸው?

**እንጸልይ፡-** ጌታ ሆይ፤ እኛ ዕቃዎቻችንና ገንዘቦቻችንን ለእግዚአብሔር መንግሥት ሥራ ሰጥተን እንድንሠራ እርዳን፤ አሜን!

1. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ

2. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት

3. እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?

4. የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና

5. ትምህርት

6. ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)

7. ፀሎት

45. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 12፥12−19 **ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፡− ኢየሱስ ወደ ኢየሩሳሌም ገባ**

12. **በማግሥቱም ለፋሲካ በዓል የመጣው ብዙ ሕዝብ ኢየሱስ ወደ ኢየሩሳሌም እየመጣ መሆኑን ሰሙ፤**

13. **የዘንባባም ዝንጣፊ ይዘው ሊቀበሉት ወጡ፤** "**ሆሣዕና**!" "**በጌታ ስም የሚመጣ ቡሩክ ነው**!" "**የእስራኤል ንጉሥ የተባረከ ነው**!" **እያሉ ይጮኹ ነበር።**

14. **ኢየሱስ የአህያ ውርንጭላ አገኘና በእርሱ ላይ ተቀመጠ፤ እንዲህ ተብሎ እንደ ተጻፈ፤**

15. "**የጽዮን ልጅ ሆይ፤ አትፍሪ፤ እነሆ፤ ንጉሥሽ በአህያ ውርንጭላ ላይ ተቀምጦ ይመጣል።**"

16. **ደቀ መዛሙርቱ ይህ ነገር በመጀመሪያ አላስተዋሉም፤ ነገር ግን ኢየሱስ ከከበረ በኋላ በዚያን ጊዜ ይህ ቃል ስለ ኢየሱስ እንደ ተጻፈና ለኢየሱስ እንደ ተደረገለት አስታወሱ።**

17. **ኢየሱስ አልዓዛርን ከመቃብር ጠርቶ ከሙታን ባስነሣበት ጊዜ፣ ከእርሱ ጋር የነበሩ ሰዎች ስለ ኢየሱስ ይመሰክሩ ነበር።** 18. **ብዙ ሰዎችም ኢየሱስ ይህን ተአምር ማድረጉን ስለ ሰሙ ሊቀበሉት ወጡ።**

19. **በዚህ ጊዜ ፈሪሳውያን፣** "**እነሆ፣ የዓለም ሕዝብ ሁሉ ኢየሱስን ተከትሎታል**! **እኛ ምንም ማድረግ እንደማንችል ታያላችሁን**?" **ተባባሉ።**

**ቁ**. 16 **ኢየሱስ በመስቀል ላይ በመሞቱና በትንሣኤው በኩል ክብርን ተቀብሎ እውነተኛ የንጉሥነትን ሥልጣን ገለጸ። በዚያን ጊዜ ደቀ መዛሙርቱ ንጉሡ ወደ ኢየሩሳሌም መግባቱን አላወቁትም። ኢየሱስ ከሞተ በኋላ ይህንን አወቁ። እኛ ደግሞ የኢየሱስ የንጉሥነት ሥልጣን አስተውለን ታዝዘናል**?

**ቁ**. 19 **እግዚአብሔር መላው ዓለም ኢየሱስን እንዲከተል ሥልጣንን ሰጠ።** (**ቁ**.32)

**ቁ**.12,13 **ኢየሱስን ለመገናኘት ሰዎች በብሉይ ኪዳን** "**ሆሣዕና በጌታ ስም የሚመጣ የተባረከ ነው**" **በማለት በጩኸት ኢየሱስን ተቀበሉ ነገር ግን እነርሱ የሚፈልጉት መሲሕ ከሮም ጭቆና ራሳቸውን ነፃ የሚያወጣ ንጉሥ ነበር። ነገር**

**ግን የእግዚአብሔር ፈቃድ ከእነርሱ ፍላጐት ይለያል። እኛ ከኢየሱስ ምንጠብቃቸው ነገሮች ምንድን ናቸው?**

**እንጸልይ፡– ጌታ ሆይ፤ ከጭቆና፣ ከሁከትና ከዓለም ችግሮች እኛን አድነን፤ አሜን!**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

46. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 12፥20−33 **ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፡− ለሁሉ ሰው ምክንያት አንድ ሰው ሞተ**

20. **በበዓሉ ጊዜ ሊሰግዱ ወደ ኢየሩሳሌም ከወጡት ሰዎች መካከል፣ አንዳንዱ የግሪክ ሰዎችም ነበሩ።**

21. **እነርሱም ከገሊላ የቤተ ሳይዳ ሰው ወደ ሆነው ወደ ፊልጶስ መጥተው፣ "ጌታዬ ሆይ፣ እኛ ኢየሱስን ማየት እንፈልጋለን" አሉት።**

22. **ፊልተስም ሄዶ ለእንድርያስ ነገረው፣ አንድርያስና ፊልጶስ አብረው ሄደው ለኢየሱስ ነገሩት።**

23. **ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰላቸው፣ "የሰው ልጅ የሚከብርበት ሰዓቱ ደርሶአል፣**

24. **እኔ በእውነት እላችኋለሁ፣ የስንዴ ቅንጣት በመሬት ላይ ወድቃ ካልሞተች፣ ብቻዋን ትቀራለች፣ ነገር ግን ከሞተች ብዙ ፍሬ ታፈራለች።**

25. **ሕይወቱን የሚወድ ያጠፋታል፣ በዚህ ዓለም ሕይወቱን የሚጠላ ግን ለዘለዓም ሕይወት ይጠብቃታል።**

26. **የሚያገለግለኝ ቢኖር ይከተለኝ፣ እኔም ባለሁበት አገልጋዬ በዚያ ይሆናል፣ የሚያገለግለኝንም አባቱ ያከብረዋል።**

27. **"አሁንስ ነፍሴ ተጨንቃለች፣ ምን ልበል? አባት ሆይ፣ ከዚህች ሰዓት አድነኝ፣ ነገር ግን እኔ የመጣሁት ለዚህች የመከራ ሰዓት ነው።** 28. **አባት ሆይ፣ ስምህን አክብረው።" ከዚያም፣ "አክብሬዋለሁ፣ ደግሞም አከብረዋለሁ" የሚል ድምፅ ከሰማይ መጣ።** 29. **በዚያ የቆሙ ሰዎች ይህን በሰሙ ጊዜ፣ "ነጐድጓድ ነው!" አሉ። ሌሎች ደግሞ፣ "መልአክ ለኢየሱስ ተናገረው" አሉ።**

30. **ኢየሱስም እንዲህ አለ፣ "ይህ ድምፅ የመጣው ስለ እኔ ሳይሆን ስለ እናንተ ነው፣**

31. **አሁን ይህ ዓለም የሚፈረድበት ጊዜ ነው፣ አሁን የዚህም ዓለም ገዢ ወደ ውጭ ይጣላል።**

32. **እኔም ከምድር ወደ ላይ ከፍ በተደረግሁ ጊዜ ሰውን ሁሉ ወደ እኔ እስባለሁ።"**

33. **ኢየሱስ ይህን የተናገረው በምን ዓይነት ሞት እንደሚሞት ለማመልከት ነበር።**

**ቁ**. 22,28−33 **ኢየሱስ በመስቀል ላይ በመሞቱ በኩል ክብርን አገኘ። የስንዴ ፍሬ ወደ ምድር ውስጥ ገብቶ ሞቶ እንደሚበቅል እንደዛው ኢየሱስ ክርስቶስ የብዙዎችን ሕይወት ለማዳን በመከራ አስቀድሞ ሞተ። ዛሬ እኛ**

በእውነት የምንፈልገው ክብር ምንድነው? ወደ ምድር ገብተን የመሞት ክብር ነው ወይስ የልባችን ምኞት?

**ቁ.** 20–22 **የግሪክ ሰዎች ኢየሱስን ለማየት መጡ። ይህ አይሁዶችንና ግሪኮችን ለማዳን ሥልጣን ያለው የወንጌል ክብር ማሳየቱ ነው። የጌታ ክብር ያለን እኛ በኀብረት ብዙ ሰዎች ወደ ጌታ እንዲመጡ የምናሳይበት መንገድ ነው።**

**ቁ.** 24–26 **ኢየሱስን መከተል ማለት የራሱን ሕይወት ሰጥቶ መከተል ማለት ነው። የስንዴ ፍሬ በምድር ወድቃ እንደሞተች ማለት ነው። እኛ ኢየሱስን ለምን ተከተልነው? እኛ እንደ ስንዴ ፍሬ ሞተን በኢየሱስ መንገድ ሄደናል?**

**እንጸልይ፦– ጌታ ሆይ፤ በየቀኑ እኛ የክርስቶስን መንገድ ተከትለን ራሳችንን በመካድ በሕይወት እንድንኖር እርዳን፤ አሜን!**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

47. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 12፥34−43 **ወር፡** **ቀን፡**

**ርዕስ፡− ኢየሱስ ዓለምን ለማዳን መጣ**

34. **ሰዎቹም፣ "በሕግ ተጽፎ የምናገኘው 'ክርስቶስ ለዘለዓለም ይኖራል' የሚል ነው፤ ታዲያ፣ አንተ፣ 'የሰው ልጅ ወደ ላይ ከፍ ማለት አለበት' እንዴት ትላለህ? ይህስ የሰው ልጅ ማን ነው?" አሉት።**

35. **ኢየሱስ እንዲህ አላቸው፤ "አሁን ለጥቂት ጊዜ ከእናንተ ጋር ብርሃን አለ፣ ጨለማ እንዳይደርስባችሁ ብርሃን ሳለላችሁ ተመላለሱ፤ በጨለማ የሚመላለስ ወዴት እንደሚሄድ አያውቅም።**

36. **ለእናንተ ብርሃን ሳለላችሁ በዚህ ብርሃን እመኑ፣ እንግዲህ እናንተ የብርሃን ልጆች ይሆናል።" ኢየሱስ ይህን ከተናገረ በኋላ ሄደና ተሰወረባቸው።**

37. **ኢየሱስም ብዙ ተአምራትን በፊታቸው ቢያደርግም እንኳ አይሁድ በኢየሱስ አላመኑም።**

38. **ይህም የሆነው ነቢዩ ኢሳይያስ፣ "ጌታ ሆይ! ምስክርነታችንን ማን አመነ? የጌታስ ኃይል ለማን ተገለጠ?" ሲል የተናገረው ቃል እንዲፈጸም ነው።**

39. **ስለዚህ ማመን አልቻሉም፣ ይህም ኢሳይያስ በሌላ ቦታ እንዲህ ሲል እንደ ተናገረው ነው፤**

40. **"ዓይናቸውን አሳውሮአል፣ ልባቸውንም አደንድኖአል፣ ስለዚህ በዓይናቸው አያዩም፣ በልባቸውም አያስተውሉም፣ እንዳልፈውሳቸውም አይመለሱም።"**

41. **ኢሳይያስ ይህን ያለው የክርስቶስን ክብር ስላየ ነው፤ ስለዚህ ይህን ስለ ኢየሱስ ተናገረ።**

42. **ሆኖም ከአይሁድ አለቆች እንኳ ብዙዎቹ በኢየሱስ አምነዋል፣ ነገር ግን ፈሪሳውያን ከምኵራብ እንዳያስወጡአቸው ስለ ፈሩ ማመናቸውን አይገልጡም ነበር፣**

43. **ይህንንም ያደረጉት በእግዚብሔር ከመመስገን ይልቅ በሰው መመስገንን ስለ ወደዱ ነው።**

**ቁ**. 34−36 **የዓለም ሕይወት የሆነው ኢየሱስ አይሁዶችን በብርሃኑ እንዲያምኑ ተናገራቸው። ብርሃን የሆነውን ኢየሱስን ቢያምኑ የብርሃን ልጆች ይሆናሉ። ብርሃን ከሆነው ከኢየሱስ ጋር የሚኖሩ ሰዎች ወደ የትኛውም ሥፍራ ቢሄዱ ከቶ በጨለማ አይሸፈኑም።**

**ቁ**. 37−41 **ኢሳያስም ስለ ኢየሱስ መምጣት ከሰባት መቶ ዓመት በፊት የኢየሱስን ክብር አይቶ ስለ እርሱ መከራና ትንሣኤ ተናገረ። ነገር ግን አይሁዶች የኢየሱስ ብዙ ምልክቶችን አይተው እርሱን አላመኑትም።**
**ቁ**. 42,43 **ሰምተው የማያምኑት ችግር አላቸው። ደግሞም ሰምተው ካመኑት በኋላ እምነትን ለሌሎች የማይገልጹት ችግር አላቸው። ኢየሱስን አምነው ነገር ግን ለመሪዎችና ለፈሪሳውያን ፈርተው ኢየሱስን ለሌሎች አልገለጹም። እነርሱ ከእግዚአብሔር የተቀበሉትን ክብር ከሰዎች የሚቀበሉት ክብር እንደሚበልጥ ዋጋ አሰቡት። እኛ በአካባቢያችን ያሉት ሰዎችን አይተን ሳንጨነቅ ደፍረን እምነታችንን ገልጸናልን**?
**እንጸልይ፡− ጌታ ሆይ፣ ሕይወታችን የሆነውን ኢየሱስን ለሌሎች ሰዎች እንድንገልጽ እርዳን፣ አሜን**!

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ**? **ማን ነው**?

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ** (**በስራ ላይ ማዋል**)

7. **ፀሎት**

48. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 12፥44−50 **ወር፡** **ቀን፡**

**ርዕስ፡− እውነተኛ እምነት**

44. **ከዚያም ኢየሱስ ድምፁን ከፍ አድርጎ እንዲህ አለ፣ "በእኔ የሚያምን በእኔ ብቻ ሳይሆን፣ በላከኝም ያምናል፣**

45. **እኔንም የሚያይ የላከኝን ያያል።**

46. **በእኔ የሚያምን ሁሉ በጨለማ እንዳይኖር እኔ ብርሃን ሆኜ ወደ ዓለም መጥቻለሁ።**

47. **ቃሌን ሰምቶ በሥራ ላይ የማያውለውን የምፈርድበት እኔ አይደለሁም፣ እኔ የመጣሁት ዓለምን ለማዳን ነው እንጂ በዓለም ላይ ለመፍረድ አይደለም።**

48. **እኔን የማይፈልግና ቃሌንም የማይቀበለውን ሰው የማፈርድበት አለ፣ እኔ የተናገርኩት ቃል በመጨረሻው ቀን እርሱን ይፈርድበታል።**

49. **እኔ ከራሴ አልተናገርሁም፣ እኔ የምናገረውን ትእዛዝ የሰጠኝ የላከኝ አብ ነው።**

50. **የእርሱም ትእዛዝ የዘለዓለም ሕይወት እንደ ሆነ አውቃለሁ። ስለዚህ እኔ የምናገረው አብ የነገረኝን ነው።"**

**ቁ**. 44,45 **ኢየሱስ እርሱን የሚያምኑትን ወደ እግዚአብሔር በእምነት እንደሚመራቸው ነገራቸው። ስለዚህ ኢየሱስን የሚያምኑ ሰዎች እግዚአብሔርን ያምናሉ። በቤተክርስቲያን ውስጥ ያለን ሰዎች ቃሉን ከወንጌላዊያን ስንቀበል እግዚአብሔርን አውቀን እንድናምን ያስፈልገናል።**

**ቁ**. 46−48 **ኢየሱስ እኛን ከጨለማ ዓለም ለማውጣት በብርሃን ወደዚህ ምድር መጣ። ስለዚህ ኢየሱስን የሚያምኑ ሰዎች ፍርሐት ጨለማው አይደለም። ኢየሱስ በእውነት የጨለማውን ሕይወት ወደ ብርሃን የሚለውጥ ነው። ኢየሱስን የሚያምኑ ሰዎች የጨለማን ሥራ አይሰሩም። እንዲሁም የጨለማን ፍሬ አያፈሩም። ብዙ ሰዎች ወደ ጨለማ ሄደው በጨለማ ውስጥ ያሉትን ሰዎች የሚለውጥ ሥራ ያደርጋሉ።**

**ቁ**. 47 **ኢየሱስ ዓለምን ለማዳን ወደ ዓለም መጣ። ስለዚህ ኢየሱስ የሚያምኑትን ሰዎች ያድናቸዋል። ነገር ግን ኢየሱስ የማያምኑትን ሰዎች ወደ ጥፋት ይልካል። ምክንያቱም ከኢየሱስ በቀር ወደ እግዚአብሔር የሚወስድ ሌላ መንገድ የለምና።** (**ዮሐ፡** 14፥6)

**ቁ.** 49,50 **ኢየሱስ በሙሉ ልብ ለእግዚአብሔር ቃልና ፈቃድ ታዘዘ። ኢየሱስ አባቱን በመታዘዝ የዘላለምን ሕይወትን አውቆ ሰበከ። እኛ ደግሞ መጽሐፍ ቅዱስ የዘላለም ሕይወት መሆኑን አውቀን እንከተላለን?**
**እንጸልይ፡- ጌታ ሆይ፤ እኛ እንደ ኢየሱስ የእግዚአብሔርን ቃልና ፈቃድ ተከትለን እንድንኖር እርዳን፤ አሜን!**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

49. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 13፥1–20 **ወር፡** **ቀን፡**

**ርዕስ፡– ኢየሱስ የደቀ መዛሙርቱን እግር አጠበ**

1. **ኢየሱስም ከአይሁድ ፋሲካ በዓል በፊት ነበር፣ ኢየሱስ ይህን ዓለም ትቶ ወደ አብ የማሄድበት ሰዓት እንደ ደረሰ አወቀ። በዚህ በዓለም ያሉትን የራሱን ወገኖች ወዶአቸው ነበር፣ እስከ መጨረሻም ወደዳቸው።**

2. **ኢየሱስና ደቀ መዛሙርቱ ራት ይበሉ ነበር፣ የስምዖን ልጅ አስቆሮታዊው ይሁዳ ኢየሱስን አሳልፎ እንዲሰጥ ዲያብሎስ በልቡ ክፉ አሳብ አሳደረበት።**

3. **ኢየሱስ አብ ሥልጣንን ሁሉ እንደ ሰጠው፣ ከእግዚብሔር እንደ ተላከና ወደ እግዚአብሔርም እንደሚመለሰ ኢየሱስ አውቆ፣**

4. **ከእራት ተነሣ፣ መጐናጸፊያውን አስቀመጠ፣ ማበሻ ጨርቅም አንሥቶ በወገቡ ታጠቀ።**

5. **ከዚህ በኋላ በመታጠቢያ ዕቃ ውሃ አድርጎ የደቀ መዛሙርቱን እግር እያጠበ በታጠቀውም ማበሻ ጨርቅ እግራቸውን ያብስ ጀመር።**

6. **ኢየሱስ ወደ ስምዖን ጴጥሮስ በመጣ ጊዜ ስምዖን ጴጥሮስ፣ "ጌታ ሆይ! አንተ የእኔን እግር ታጥባለህን? አለው።**

7. **ኢየሱስም መልሶ፣ "እኔ የማደርገውን አሁን አታውቅም፣ በኋላ ግን ታስተውላለህ" አለው።**

8. **ጴጥሮስም "አንተ የእኔን እግር ከቶ አታጥብም!" አለው። ኢየሱስም "እኔ እግርህን ካላጠብኩህ ከእኔ ድርሻ የለህም" አለው።**

9. **ስምዖን ጴጥሮስም፣ "ጌታ ሆይ፣ እንግዲያውስ እግሬን ብቻ ሳይሆን እጄንም ራሴንም እጠበኝ" አለው።**

10. **ኢየሱስም፣ "ሰውነቱን የታጠበ ሁለመናዉም ንጹሕ በመሆኑ እግሩን ከመታጠብ በቀር ሌላ አያስፈልገውም፣ እናንተም ንጹሖች ናችሁ፣ ነገር ግን ሁላችሁም ንጹሖች አይደላችሁም" አለው።**

11. **ኢየሱስ፣ "ሁላችሁም ንጹሖች አይደላችሁም" ያለው አሳልፎ የሚሰጠው ማን እንደ ሆነ ያውቅ ስለ ነበር ነው።**

12. **ኢየሱስ እግራቸውን ካጠበ በኋላ ልብሱን ለበሰና ወደ ቦታው ተመልሶ ተቀመጠ፣ እንዲህም አላቸው፣ "ምን እንዳደረግሁላችሁ አስተዋላችሁ?**

13. እናንተ ‘መምህርና ጌታ’ ትሉኛላችሁ፣ ትክክል ነው፣ እንደምትሉኝ እንዲሁ ነኝና።
14. እንግዲህ እኔ ጌታችሁና መምህራችሁ ስሆን እግራችሁን ካጠብኩ እናንተም እርስ በርሳችሁ እግራችሁን መተጣጠብ ይገባችኋል።
15. እኔ ለእናንተ እንዳደረግሁት እናንተም እንድታደርጉ ምሳሌ ሰጥቻችኋለሁ።
16. በእውነት እላችኋለሁ፣ አገልጋይ ከጌታው አይበልጥም፣ መልእክተኛም ከላኪው አይበልጥም።
17. እናንተ እንግዲህ እነዚህን ነገሮች አውቃችሁ ብትፈጽሙ ትባረካላችሁ።
18. ይህን የምናገረው ስለ ሁላችሁም አይደለም፣ እኔ የመረጥኳችሁን አውቃለሁ፣ ነገር ግን ‘እንጀራዬን የበላ በእኔ ላይ በጠላትነት ተነሣብኝ’ የሚለው የመጽሐፍ ቃል እንዲፈጸም ነው።
19. ይህ ከመሆኑ በፊት አሁን አስቀድሜ የምነግራችሁ፣ ከተፈጸመ በኋላ፣ በእኔ ማንነት እንድታምኑ ነው።
20. በእውነት እላችኋለሁ፣ እኔ የምልከውን የሚቀበል እኔን ይቀበላል፣ እኔንም የሚቀበል የላከኝን ይቀበላል።”

**ቁ.** 1,4,5 ኢየሱስ የደቀ መዛሙርቱን እግር በማጠቡ እነርሱን በሙሉ መውደዱን አሳየ። በዚያን ጊዜ የእግር ማጠቡ ሥራ ባሪያዎች ብቻ ነበር። ስለዚህ የኢየሱስ ሥራ ለእነርሱ ድንጋጤ ነበር። ነገር ግን መምህርና ጌታ የሆነው ኢየሱስ ራሱ የደቀ መዛሙርቱ አገልጋይ በመሆን እነርሱን አገለገላቸው። ደግሞ ኢየሱስ እኛን ለማገልገል እንደዚህ ራሱን አዋርዶ በጥልቀት ያስባል።

**ቁ.** 2,11 የአስቆሮቱ ይሁዳ በሥጋ ኢየሱስን ተከተለ። ነገር ግን የአስቆሮቱ ይሁዳ አእምሮ ሰይጣን ተቆጣጥሮ ነበር። እርሱም ኢየሱስን አያምንም። እርሱም ኢየሱስን እየተከተለ ሁል ጊዜ ገንዘብን ይወዳል። (ዮሐ12፥6) ለራሱ ብዙም የሚጠቅም አይደለም። ስለዚህ የአስቆሮቱን ይሁዳ ኢየሱስን ለአይሁዶች አሳልፎ የሰጠው በራሱ አሳብ ነው። ለእኛ ደግሞ

የሚያስፈልገን ገንዘብ ነውን? ወይስ ጥሩ ዕቃዎች ናቸው? ወይስ ኢየሱስ? የትኛው ነው?

**ቁ**. 6−10 ኢየሱስን የማያምኑ ሰዎች ከእግዚአብሔር ጋር ግንኙነት የላቸውም። ዛሬ ሕይወታችንን ሁሉ በንጽሕና ከእግዚአብሔር ጋር ለቅን ግንኙነት ሰጥተናልን?

**እንጸልይ፦** ጌታ ሆይ፤ በመስቀል ላይ እስከሞት ድረስ ኢየሱስ ለእኛ የሰጠኸው ፍቅርህንና ፀጋህን ለሌሎች እንድናካፍል እርዳን፤ አሜን።

1. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ

2. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት

3. እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?

4. የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና

5. ትምህርት

6. ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)

7. ፀሎት

8. 50. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 13፥21–30 **ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፡– የአስቆሮንቱ ይሁዳ አሳልፎ የመስጠት ቅጣትና ማስታወቂያ**

21. **ኢየሱስ ይህን ካለ በኋላ በመንፈሱ ታውኮ፣ "በእውነት እላችኋለሁ፣ ከእናንተ አንዱ አሳልፎ ይሰጠኛል" ሲል ገልጦ ተናገረ።** 22. **ደቀ መዛሙርቱ ይህን ስለ ማን እንደ ተናገረ ባለማወቃቸው እርስ በርሳቸው ተያዩ።**

23. **ኢየሱስ ይወደው የነበረው፣ ከደቀ መዛሙርቱ አንዱ በኢየሱስ ደረት ተጠግቶ ተቀምጦ ነበር።**

24. **ስምዖን ጴጥሮስ ይህን ደቀ መዝሙር ጠቀሰና፣ "ስለ ማን እንደ ተናገረ እስቲ ጠይቅ" አለው።**

25. **እርሱም ወደ ኢየሱስ ደረት እንዲህ ተጠግቶ፣ "ጌታ ሆይ፣ ማን ይሆን" ብሎ ጠየቀው።**

26. **ኢየሱስም፣ "ይህን ቍራሽ እንጀራ ከወጭቱ አጥቅሼ የምሰጠው እርሱ ነው" አለው፤ ከዚያም ቍራሹን እንጀራ አጥቅሶ ለስምዖን ልጅ ለአስቆሮቱ ይሁዳ ሰጠው።** 27. **ይሁዳም ቍራሹን እንጀራ እንደ ተቀበለ ወዲያው ሰይጣን ገባበት። ኢየሱስም ይሁዳን፣ "የምታደርገውን ቶሎ አድርግ" አለው፤**

28. **ነገር ግን ኢየሱስ ለምን እንዲህ እንዳለው በማዕድ ከተቀመጡት ማንም አላወቀም።**

29. **ይሁዳ ገንዘብ ያዥ ስለ ነበረ፣ አንዳንዶቹ ለበዓሉ የሚያስፈልግ ነገር እንዲገዛ ወይመ ለድሆች እንዲሰጥ ኢየሱስ የተናገረው መሰላቸው።**

30. **ይሁዳም ያን ቍራሽ እንጀራ እንደ ተቀበለ ወጥቶ ሄደ፤ ጊዜውም ሌሊት ነበረ።**

**ቁ.** 23–25 **ኢየሱስ ለዮሐንስ የጌታን ፍቅር ተናገረ። እኛ ከጌታ ጋር ምን ዓይነት ግንኙነት አለን? በየቀኑ በቃሉ በኩል ከጌታ ጋር በቅርብ ፍቅር እንደ እግዚአብሔር ፈቃድ እንኖራለን?**

**ቁ.** 22–29 **ደቀ መዛሙርቱም ከእነርሱ መካከል ማን ኢየሱስን አሳልፎ እንደሚሰጥ አያውቁም። እነርሱ ኢየሱስ የተናገረውን ቃልና ምልክቶችን አላስተዋሉም። ምክንያቱም ለእነርሱ መንፈሳዊ ማስተዋል የላቸውም። እኛ ደግሞ እንደ ደቀ መዛሙርቱ በቤተ ክርስቲያን ውስጥ እያለን ከጌታ መንገድ ወደሚያጠፋን አልሄድንምን?**

**ቁ**. 30 **የአስቆሮንቱ ይሁዳ ኢየሱስን አሳልፎ ለመስጠት የእንጀራ ቁራሽ ወስዶ የሄደው በለሊት ነበር። ይህ ለሊት ማለት የአስቆሮንቱን ይሁዳ መንፈሳዊ ሁኔታ ይናገራል። ከቃሉ ይልቅ ገንዘቡን መውደዱና ከጌታ ራሱን አስበልጦ የመውደዱ ሕይወት ወደ ጨለማ ውስጥ ያስገባል። እኛ እንደ አስቆሮንቱ ይሁዳ ሳንሆን ብርሃን በሆነው ጌታ ውስጥ ልንኖር ያስፈልጋል።**

**እንጸልይ፦ ጌታ ሆይ፣ የአለም ዕቃዎችና ገንዘብን ትተን ብርሃን በሆነው በኢየሱስ ውስጥ እንድንኖር እርዳን፣ አሜን**!

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ**? **ማን ነው**?

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ** (**በስራ ላይ ማዋል**)

7. **ፀሎት**

51. **የንባብ ክፍል  ዮሐንስ** 13፥31−38 **ወር፡             ቀን፡**

**ርዕስ፡− አዲስ የፍቅር ትእዛዛት**

31. ይሁዳ ወጥቶ ከሄደ በኋላ ኢየሱስ እንዲህ አለ፤ “አሁን የሰው ልጅ ከበረ፤ በእርሱም እግዚአብሔር ከበረ።

32. እንግዲህ እግዚአብሔር በእርሱ ከከበረ፣ እግዚአብሔር ልጁን በራሱ ዘንድ ያከብረዋል፤ ወዲያውም ያከብረዋል።

33. ልጆቼ ሆይ፣ ከእናንተ ጋር የምቈየው ለጥቂት ጊዜ ነው፤ እናንተም ትፈልጉኛላችሁ፤ ለአይሁድ፣ ‘እኔ ወደምሄድበት ልትመጡ አትችሉም’ እንዳልኋቸው፣ አሁንም ለእናንተ ይህንኑ እላችኋለሁ።

34. አዲስ ትእዛዝ እሰጣችኋለሁ፤ ይኸውም እርስ በርሳችሁ እንድትዋደዱ ነው፤ እንግዲህ እኔ እንደ ወደድኋችሁ እናንተም እርስ በርሳችሁ ተዋደዱ።

35. እርስ በርሳችሁ ብትዋደዱ፣ ሰዎች ሁሉ የእኔ ደቀ መዛሙርት እንደ ሆናችሁ በዚህ ያውቃሉ።

36. ስምዖን ጴጥሮስ ኢየሱስን፣ “ጌታ ሆይ፣ የምትሄድው ወዴት ነው?” ሲል ጠየቀው። ኢየሱስም፣ “እኔ ወደምሄድበት አሁን ልትከተለኝ አትችልም፤ በኋላ ግን ትከተለኛለህ” ሲል መለሰለት።

37. ጴጥሮስም፣ ጌታ ሆይ፣ አሁን ልከተልህ የማልችለው ስለ ምንድር ነው? ስለ አንተ ሕይወቴንም ቢሆን አሳልፌ እሰጣለሁ አለው። 38. ኢየሱስ፣ እንዲህ ሲል መለሰ፣ “ሕይወትህን በእርግጥ ለእኔ አሳልፈህ ትሰጣለህን? በእውነት እልሃለሁ፤ዶሮ ሳይጮኽ ሦስት ጊዜ ትክደኛለህ።”

**ቁ**. 31,32   ኢየሱስ በመስቀል ላይ መሞት መከራ ሳይሆን ክብር ነው።

**ቁ**. 33−35   ኢየሱስ በክብር ከፍ ከፍ እያለ ከደቀ መዛሙርቱ አጠገብ ወጥቶ ወደ ሰማይ ሄደ። ኢየሱስ ወደ እግዚአብሔር ሄዶ እንደገና እስኪ መለስ ድረስ አንዳንድ ጊዜ በዓለም ላሉት ደቀ መዛሙርቶች አዲስ የፍቅር ትእዛዞችን ሰጠ። ደቀ መዛሙርቱ ብቻቸውን እየተወዳዱ ከጌታ ጋር እያሉ ለዓለም እንዲገልጹ ምክንያት ሆነዋል። ጌታ በእኛ በኩል ለዚህ ዓለም ሰዎች ራሳችንን እንድንገልጽ ይፈልጋል።

**ቁ**. 36−38 **ኢየሱስ ጴጥሮስን እርሱ ደካማነቱን በንሰሓ ተመልሶ በመጨረሻ እርሱን በድፍረት መከተሉን ያውቃል። የእኛንም ድካም ኢየሱስ ያውቀዋል። ስለዚህ ከአፋችን በሚወጣው የንሰሓ ፍሬን እንድናፈራ ጌታን እናምናለን።**
**ቁ**. 34,35 **እኛ እርስ በርሳችን እንድንዋደድ መሰረቱ ኢየሱስ ለእኛ ባሳየው በመስቀል ላይ በተሰቀለው ፍቅር ነው። ኢየሱስ የደቀ መዛሙርቱን እግር ያጠበው ደቀ መዛሙርቱም ሌሎች ሰዎችን እንዲያገለግሉ ፈልጎ ነው። ከእኛ እንደ ኢየሱስ በፍቅር የሚያደርግ ሰው ማን ነው**?
**እንጸልይ፡− ጌታ ሆይ፤ ኢየሱስ ሰዎችን እንደወደደ እኛም ደግሞ ጐረቤቶቻችንን እንድንወድድ እርዳን፤ አሜን**!

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ**? **ማን ነው**?

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ** (**በስራ ላይ ማዋል**)

7. **ፀሎት**

52. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 14፥1−14 **ወር፡** **ቀን፡**

## ርዕስ፦ ወደ እግዚአብሔር የሚያደርሰው መንገድ

1. **ቀጥሎም ኢየሱስ እንዲህ አለ፤ "ልባችሁ አይጨነቅ፤ በእግዚአብሔር እመኑ፤ በእኔም እመኑ፤**

2. **በአባቴ ቤት ብዙ መኖሪያ አለ፤ ይህ ባይሆንማ ኖሮ ባልኋችሁ ነበር፤ 'የምትኖሩበትን ስፍራ ላዘጋጅላችሁ እሄዳለሁ'**

3. **ሄጄም ስፍራ ካዘጋጀሁላችሁ በኋላ፣ እኔ ባለሁበት እናንተም ከእኔ ጋር እንድትኖሩ እንደገና መጥቼ እወስዳችኋለሁ።**

4. **እኔ ወደምሄድበትም ስፍራ መንገዱንም ታውቃላችሁ።"**

5. **ቶማስም፣ "ጌታ ሆይ፤ ወዴት እንደምትሄድ አናውቅም፤ ታዲያ፣ መንገዱን እንዴት ማወቅ እንችላለን?" አለው።**

6. **ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰለት፤ "እኔ መንገድና እውነት ሕይወትም ነኝ፤ በእኔ በኩል ካልሆነ በቀር ማንም ወደ አብ የሚመጣ የለም።**

7. **እናንተ እኔን ብታውቁኝ ኖሮ አባቴንም ባወቃችሁት ነበር። ከአሁን እናንተ አባቴን ታውቁታላችሁ፤ አይታችሁታልም።"**

8. **ፊልጶስም፣ "ጌታ ሆይ፤ አብን አሳየንና ይበቃናል" አለው።**

9. **ኢየሱስም እንዲህ አለው፤ "አንተ ፊልጶስ! ይህን ያህል ጊዜ ከእናንተ ጋር ስኖር አታውቀኝምን? እኔን ያየ አብን አየቶአል፤ እንዴትስ፣ 'አብን አሳየን' ትላለህ?**

10. **እኔ በአብ እንዳለሁ፣ አብም በእኔ እንዳለ አታምንምን? ለእናንተ የምናገረውን ቃል የምናገረው በራሴ ቃል አይደለም፤ ነገር ግን ሥራውን ሁሉ የሚሠራው፣ በእኔ የማኖረው አብ ነው።**

11. **እኔ በአብ እንዳለሁ፣ አብ በእኔ እንዳለ እመኑ፤ ባይአመኑ በሥራዎቼ ምክንያት እመኑኝ።**

12. **በእውነት እላችኋለሁ፤ በእኔ የሚያምን እኔ የምሠራውን ሥራ ይሠራል፤ እንዲያውም ከዚህ የበለጠ ይሠራል፤ እኔ ወደ አብ እሄዳለሁ።**

13. **አብ በወልድ እንዲከብር፣ በስሜ የምትለምኑትን ሁሉ አደርገዋለሁ፤**

14. **እናንተ ማንኛውን ነገር በስሜ ብትለምኑኝ፣ እኔ አደርገዋለሁ።**

**ቁ.** 1 **ኢየሱስ የደቀ መዛሙርቱ ልብ እንዳይታወክ እምነትን ሰጠ። ኢየሱስ ደቀ መዛሙርቱ ስለ ፈሩ በቃሉ በኩል መጽናናትን ሰጠ። እኛም ደግሞ እንደ ደቀ መዛሙርት በእምነት ከኢየሱስ ጋር ስንኖር መጽናናትን እናገኛለን።**

**ቁ.** 2-4 **ኢየሱስ ደቀ መዛሙርቱን ትቶ መሄዱን ኢየሱስ በመስቀል ላይ ሞቶ የእኛን ኃጢአት አስወግዶ ከእግዚአብሔር ጋር አስታርቆ ከአባቱ ጋር ኅብረት እንዲኖር አደረገ ማለት ነው።** (**ዮሐ.** 14፥6)

**ቁ.** 12-14 **ኢየሱስ ደቀ መዛሙርቶችን ትቶ ሄደ። ነገር ግን ለእነርሱ ትልቅ ሥልጣን ሰጥቶ የእግዚአብሔርን ሥራ እንዲቀጥሉ አደረገ። እነዚህን ሥልጣኖችን ተቀብለን በዓለም ታላቅ ሥራ ብንሠራ ማንኛውንም ነገር በኢየሱስ ስም ብንጸልይ እርሱ ያደርግልናል። ኢየሱስ በራሱ ስም ወደ አባቱ ለሚጸልዩ ሰዎች ይመልሳል። ምክንያቱም በቁጥር** 13 **ላይ "እናንተ በእኔ ስም ማንኛውንም ነገር ብትለምኑ እኔ አደርገዋለሁ" ብሏልና። እኛም ወደ ጌታችን የትኛውን ነገር ይዘን ሄደናል**?

**ቁ.** 5,8 **የኢየሱስን ቃል ያላስተዋሉ ቶማስና ፊልጶስ በቅንነት የራሳቸውን ችግር ገልጸው ምላሽን ተቀበሉ። እኛ ደግሞ በሕይወታችን ጥያቄ አለን**? **እኛ በሕይወታችን መጽሐፍ ቅዱስን ስናነብብ ብዙ ጥያቄ የተፈጠሩትን መጋቢዎችንና ወንጌላውያንን ጠይቀን ልንረዳ ያስፈልጋል።**

**እንጸልይ፡- ጌታ ሆይ፣ ዛሬ እኛ በምንጸልየው ጸሎት በኩል ታላቅ ሥራን እንድናደርግ እርዳን፣ አሜን**!

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

53. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 14፥15−24 **ወር፡ ቀን፡**

**<u>ርዕስ፦ የኢየሱስ መመለስ</u>**

15. **እናንተ ብትወዱኝ ትእዛዜን ትጠብቃላችሁ።**

16. **እኔ አብን እለምናለሁ፣ እርሱም ከእናንተ ጋር ለዘላለም የሚኖር ሌላ አጽናኝ ይሰጣችኋል፣**

17. **እርሱም የእውነት መንፈስ ነው፣ ዓለም እርሱን ስለማያየውና ስለማያውቀው ሊቀበለው አይችልም። እናንተ ግን፣ እርሱ ከእናንተ ጋር ስለሚኖርና በውስጣችሁ ስላለ ታውቁታላችሁ።**

18. **እኔ ወላጅ እንደሌላቸው ልጆች አልተዋችሁም፣ ተመልሼ ወደ እናንተ እመጣለሁ።** 19. **ከጥቂት ጊዜ በኋላ፣ ዓለም ከቶ አያየኝም፣ እናንተ ግን ታዩኛላችሁ። እኔ ሕያው ስለ ሆንሁ እናንተም ሕያዋን ትሆናላችሁ።** 20. **እኔ በአብ እንዳለሁ፣ እናንተም በእኔ እንዳላችሁ፣ እኔም በእናንተ እንዳሁ በዚያን ቀን ታውቃላችሁ።** 21. **እኔን የሚወደኝ ትእዛዜን ተቀብሎ የሚጠብቅ ነው፣ እኔንም የሚወደኝን አባቴ ይወደዋል፣ እኔም እወደዋለሁ፣ ራሴንም እገልጥለታለሁ።”** 22. **አስቆሮታዊው ሳይሆን ሌላው ይሁዳ፣ “ጌታ ሆይ! ራስህን ለዓለም ሳይሆን ለእኛ የምትገልጠው እንዴት ነው?” አለው።** 23. **ኢየሱስ እንዲህ ሲል መለሰለት፣ “እኔን የሚወደኝ ቃሌን ይጠብቃል፣ አባቴም ይወደዋል፣ እኛ ወደ እርሱ መጥተን ከእርሱ ጋር አብረን እንኖራለን።**

24. **እኔን የማይወደኝ ቃሌን አይጠብቅም፣ እናንተ ይህ የምትሰሙት ቃል የላከኝ የአብ ነው እንጂ የእኔ አይደለም።**

**ቁ**. 16,18 **ኢየሱስ የራሱን ሰዎች በዓለም ውስጥ ሳይጥላቸው በመንፈስ ቅዱስ በኩል እንደገና ለመውሰድ ይመለሳል። ኢየሱስ በመስቀል ላይ ሞቶ ደቀ መዛሙርቱን ተወ። ነገር ግን በሦስተኛው ቀን ከሞት ተነሥቶ ወደ ሰማይ ሄደ። ደግሞም ጌታ በመንፈስ ቅዱስ በኩል በደቀ መዛሙርቱ ውስጥ ለዘላለም ይኖራል። የእግዚአብሔርንም ሥራ እንዲቀጥሉ አደረገ። ደግሞም ኢየሱስን የምናምን እኛን አይተወንም። ፍጹም እንድንረዳ መንፈስ ቅዱስን ይሰጠናል። እኛ የጌታን ሥራ እንድናደርግ በእኛ ውስጥ ሥልጣንና ጥበብን ይሰጠናል። በዚህም በመንፈስ ቅዱስ ይበልጥ እየተበረታታን እንመካለን።**

**ቁ**. 17 **ከኢየሱስ የተላከው መንፈስ ቅዱስ ደግሞ የእውነት መንፈስ ነው። ስለዚህ የእውነት መንፈስ በእኛ መካከል ሲኖር እኛ ጌታን በደንብ አውቀን ተቀብለን እንድንመሰክር ይረዳናል። ነገር ግን ዓለም ይህ የእውነት መንፈስን አልተቀበለም። ጌታንም ስለማያውቅ አያምንም። በመጨረሻም ለፍርድና ለጥፋት ይሆናል።**

**ቁ**. 15,21 **ኢየሱስን የሚወድዱ ሰዎች የጌታን ትእዛዛትን ይጠብቃሉ። እግዚአብሔርንም ለሚወድዱ ሰዎች የእግዚአብሔር ቃል ከቶ አይከብዳቸውም።** (1ኛ ዮሐ. 5፥3) **እኛ ጌታን እንዴት እንወደዋለን**? **በእኛ አጠገብ ያሉት ሰዎች እኛን ክርስቲያኖችን ምን ዓይነት ሰዎች እንደሆንን ያውቃሉ**?

**እንጸልይ፦ ጌታ ሆይ፤ የእግዚአብሔርን ፍቅር ለጐረቤቶቻችን እንድንገልጽ እርዳን፤ አሜን**!

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ**? **ማን ነው**?

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ** (**በስራ ላይ ማዋል**)

7. **ፀሎት**

54. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 14፥25−31 **ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፡− ከአባቱ የተሰጠ ስጦታ**

25. "**አሁን ከእናንተም ጋር እያለሁ ይህን ነገር ነግሬአችኋለሁ፤**

26. **አብ በእኔ ስም የሚልከው አጽናኙ መንፈስ ቅዱስ ግን ሁሉን ነገር ያስተምራችኋለሁ፤ እኔ የነገርኋችሁንም ሁሉ እንድታስታውሱ ያደርጋችኋል።**

27. "**ሰላምን እተውላችኋለሁ፤ ሰላሜንም እሰጣችኋለሁ፤ እኔ የምሰጣችሁ ሰላም ዓለም እንደሚሰጠው ዓይነት አይደለም፤ ልባችሁ አይጨነቅ፤ ደግሞም አይፍራ።**

28. '**እኔ እሄዳለሁ፤ ተመልሼም ወደ እናንተ እመጣለሁ**' **ማለቴን ሰምታችኋል፤ አባት ከእኔ ስለሚበልጥ እናንተ ብትወዱኝስ ኖሮ ወደ አብ በመሄዴ ደስ ባላችሁ ነበር።**

29. **ይህ በሚሆንበት ጊዜ እንድታምኑ፤ ከመሆኑ በፊት አስቀድሜ እኔ ለእናንተ ነግሬአችኋለሁ።**

30. **የዚህ ዓለም ገዥ ሰይጣን መምጣቱ ስለ ሆነ ከእንግዲህ ወዲህ ከእናንተ ጋር ብዙ አልነጋገርም። እርሱ በእኔ ላይ ምንም ሥልጣን የለውም፤**

31. **ነገር ግን እኔ አብን እንደምወድ፤ አባቴ ያዘዘኝንም እንደ ማደርግ ዓለም እንዲያውቅ ነው።** "**ተነሡ፤ ከዚህ እንሂድ።**"

**ቁ.** 26 **እግዚአብሔር ለኢየሱስ መንፈስ ቅዱስን ሰጥቶ እንደ አባት አስተማረ እኛንም ደግሞ ያስተምረናል። ኢየሱስ ከራሱ ሳይሆን አባቱ እርሱን እንዳስተማረው የአባቱን ትምህርት ለእኛ ይሰጣል።** (**ዮሐ.** 7፥16−18፤ 14፥10) **ደግሞም መንፈስ ቅዱስ በእኛ ውስጥ ሆኖ የኢየሱስን ቃል እንድናስተውልና እንድንታዘዝ ያደርጋል።**

**ቁ** 27,28 **ኢየሱስ የሚሰጠው ሠላም ዓለም ከሚሰጠው ሰላም ይለያል። ኢየሱስ ሁል ጊዜ በእግዚአብሔር መገኘት በኩል ሰላምን ያኖራል። ደግሞ እኛ በእግዚአብሔር መገኘት በኩል በሠላም እንድንኖር ይፈልጋል። እኛ በጌታ ውስጥ ያለንና ጌታ በእኛ ውስጥ የሚኖር እኛም ዓለም ሳያውቀን በሠላም እንኖራለን። ታዲያ ዛሬ ሠላም ነው?**

**ቁ.** 30 **ኢየሱስ በዚህ ምድር ከማንኛውም አለቃ ወይም ገዥ ይልቅ ሥልጣን አለው። ኢየሱስ በመስቀል ላይ የመሞቱ ሁናቴ የዓለም ገዥዎች ሥልጣን ለመጫን አይደለም። እግዚአብሔር በመስቀሉ በኩል ዓለምን ለማዳን የእነርሱን**

ወይም የዓለም ገዥዎችን ሥልጣን ተጠቅሟል። ስለዚህ ማንኛውም የዓለም ሥልጣን የእግዚአብሔርንና የኢየሱስን ሥራ አይከለክልም።
ቁ. 31 ኢየሱስ በመስቀል ላይ እስኪሞት ድረስ የእግዚአብሔርን ፈቃድ ታዘዘ። እኛ ደግሞ ከኢየሱስ የመታዘዝን ሕይወት እንማራለን።
እንጸልይ፡– ጌታ ሆይ፤ የእግዚአብሔርን ቃል ታዘን በእምነትና በፍቅር እንድንኖር እርዳን፤ አሜን!

1. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ

2. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት

3. እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?

4. የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና

5. ትምህርት

6. ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)

7. ፀሎት

55. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 15፥1-8 **ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፡- ኢየሱስ እውነተኛ የወይን ግንድ ነው**

1. "**እውነተኛ የወይን ግንድ እኔ ነኝ፣ አትክልተኛውም አባቴ ነው፣**
2. **በእኔ ያለውን ፍሬ የማያፈራውን ቅርንጫፍ ሁሉ አባቴ ቈርጦ ይጥለዋል፣ ፍሬ የሚያፈራውን ቅርንጫፍ ግን አብዝቶ እንዲያፈራ ገርዞ ያጠራዋል።**
3. **እናንተም ስለ ነገርኋችሁ ቃል አሁን ንጹሐን ናችሁ።**
4. **በእኔ ኑሩ፣ እኔም በእናንተ እኖራለሁ። ቅርንጫፍ በወይኑ ግንድ ካልሆነ በቀር ብቻውን ፍሬ ሊያፈራ አይችልም፣ እናንተም በእኔ ካልኖራችሁ ፍሬ ልታፈረ አትችሉም።**
5. "**እኔ የወይን ተክል ነኝ፣ እናንተም ቅርንጫፎች ናችሁ። ማንም በእኔ ቢኖር እኔም በእርሱ ብኖር፣ እርሱ ብዙ ፍሬ ያፈራል፣ ነገር ግን ያለ እኔ ምንም ልታደርጉ አትችሉም።**
6. **በእኔ የማይኖር እርሱ እንደ ቅርንጫፍ ወደ ውጭ ተጥሎ ይደርቃል፣ ሰዎች እንዲህ ያሉት ቅርንጫፎች ተሰብስበው ወደ እሳት ይጣሉና ይቃጠላሉ።**
7. **በእኔ ብትኖሩ ቃሌም በእናንተ ቢኖሩ፣ እናንተ የምትፈልጉትን ማንኛውንም ነገር ለምኑ፣ ይሰጣችኋል።**
8. **እናንተ ብዙ ፍሬ ብታፈሩ ደቀ መዛሙርቴ መሆናችሁን ብትገልጡ፣ በዚህ አባቴ ይከብራል።**

**ቁ**. 3 **ኢየሱስ በቃሉ እኛን አንጽቶ ነጻ አደረገ። ይህ ማለት በመንፈስ ቅዱስ ሥራ በኩል ሁለተኛ ልደትን ተቀበልን ማለት ነው። እኛ ኢየሱስ ባስተማረው ትምህርት በእምነታችን ነጻን ማለት ነው። እነዚያ በኢየሱስ ቃል ቀድመው የነጹ ሰዎች ከእግዚአብሔር አይቆረጡም።**

**ቁ**. 4-6 **ኢየሱስ እውነተኛ የወይን ግንድ ነው። ስለዚህ የወይኑ ግንድ የሆነው ኢየሱስ እኛ በደንብ ተያይዘን ኢየሱስ የሚሰጠውን ብዙ ቤዛነትን ሕይወትን ተቀብለን እግዚብሔርን በመፈለግ መልካም ፍሬ እንድናፈራ ወለደን። ለምሳሌ፡- የወይን ግንድ ቅርንጫፉን በመጠበቅ ወይኑ እንዲያፈራ እንደሚያደርግ እንደዚያው ኢየሱስ እኛን በመጠበቅ መንፈስ ቅዱስ በኩል እኛ ብዙ መልካም ፍሬ እንድናፈራ ያደርጋል።**

**ቁ**. 7, 8 በኢየሱስ ጥልቅ ሕብረት የሚኖሩ ሰዎች ሁሉ በሥራቸው ሳይፈሩ በጌታ ቃል ተከትለው ወደ እግዚአብሔር በሚጸልዩበት ጊዜ ታላቅ ሥልጣንን ይቀበላሉ። በእንደዚህ ዓይነት ሕብረት የሚኖሩ የራሳቸውን ኀይልና መልካም ፍሬን ለመውሰድ ወደ ብዙ ቦታዎች አይሮጡም። ነገር ግን በቃሉ ጥልቅ ስለጸኑ በጸሎት በኩል ብዙ ፍሬን ይወስዳሉ።
እንጸልይ፡– ጌታ ሆይ፤ እኛ በኢየሱስ ጥልቅ ሕብረት እንድንኖር፣ ጌታንም እንድናስደስትና ብዙ መልካፍ ፍሬን እንድናፈራ እርዳን፤ አሜን!

1. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ

2. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት

3. እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?

4. የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና

5. ትምህርት

6. ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)

7. ፀሎት

56. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 15፥9−17 **ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፦ እርስ በርሳችሁ ተዋደዱ**

9. **አብ እኔን እንደ ወደደኝ እኔም እናንተን ወደድኳችሁ፣ ስለዚህ በፍቅሬ ኑሩ።**

10. **እኔ የአባቴን ትእዛዝ ጠብቄ በፍቅሩ እንደምኖር፣ እናንተም ትእዛዜን ብትጠብቁ በፍቅሬ ትኖራላችሁ።**

11. **ይህን የነገርኳችሁ ደስታዬ በእናንተ እንዲሆንና የእናንተም ደስታ ፍጹም እንዲሆን ነው።**

12. **የእኔ ትእዛዝ ይህች ናት፣ እኔ እናንተን እንደ ወደድኋችሁ እናንተም እርስ በርሳችሁ ተዋደዱ።**

13. **ሰው ሕይወቱን ስለ ወዳጆቹ አሳልፎ ከመስጠት የበለጠ ፍቅር የለውም።**

14. **እናንተም እኔ የማዛችሁን ብትፈጽሙ ወዳጆቼ ናችሁ።**

15. **ከእንግዲህ አገልጋዮች አልላችሁም፣ አገልጋይ ጌታው የሚሠራውን አያውቅምና፣ ነገር ግን ከአባቴ የሰማሁትን ሁሉ ስለ ገለጽሁላችሁ ወዳጆች ብያችኋለሁ።**

16. **እኔ መረጥኋችሁ እንጂ እናንተ አልመረጣችሁኝም፣ ሄዳችሁ ብዙ ፍሬ እንድታፈሩ፣ ፍሬያችሁም እንዲኖር ሾምኋችሁ። ስለዚህ በስሜ የምትለምኑትን ሁሉ አብ ለእናንተ ይሰጣችኋል።**

17. **ትእዛዜ ይህቺ ናት፣እርስ በርሳችሁ እንድትዋደዱ ነው።**

**ቁ**. 9,13,15 **ከእግዚአብሔር ፍቅር የተቀበለው ኢየሱስ በፍቅሩ የራሱን ሰዎችን በመውደድ ነው። ኢየሱስ ፍቅር ደቀ መዛሙርቱን ሲጠራ ባሮች እንዲሆኑ አይደለም። ነገር ግን ወዳጆች እንዲሆኑ ጠራቸው። ኢየሱስ ወዳጆቹን በመውደድ የራሱን ሕይወት ሰጠ። ዛሬ እኛም የኢየሱስ ወዳጆች የሆኑትን ጠርተን እንቀበላለን።**

**ቁ**. 16 **ኢየሱስ በሥልጣኑ እኛን መረጠ። ምክንያቱም እኛ ሁል ጊዜ ብዙ መልካፍ ፍሬን እንድናፈራ ፈልጎ ነው። ይህ ቃል “ሾመ” ማለት ኢየሱስ ለእኛ የሰጠውን ሥራ ስናደርግ የእግዚአብሔር ሥልጣንና እውቀት ተሰጥቶልናል ማለት ነው።**

**ቁ**. 12,14,17 **የኢየሱስ ወዳጆች በእርሱ ፍቅር የሚኖሩና በእርሱ ትእዛዝ የሚታዘዙ ሰዎች ናቸው። ኢየሱስ ደቀ መዛሙርቱን ወዳጆቹ ብሎ ጠርቶ የፍቅር**

ትእዛዞችን ሰጠ። እነርሱም እርስ በርሳቸው እንዲዋደዱ በሕይወታቸው በኩል የኢየሱስ ወዳጅነትን እንዲለማመዱ ነው። እኛ በእውነት የኢየሱስ ወዳጆች ነን? እኛ በጌታ ፍቅር ብንዋደድ ለወንድሞቻችንና ለእህቶቻችን ጊዜያችንን፣ ገንዘባችንን ሰጥተን ወድደናቸዋልን? የጌታን ፍቅር ለማን እንዴት አደረግን? እንጸልይ፦ ጌታ ሆይ፤ እኛን አንተ እንደወደድክ እኛም ደግሞ በአንተ ፍቅር ወንድሞቻችንንና እህቶቻችንን እንድንወድድ እርዳን፤ አሜን!

1. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ

2. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት

3. እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?

4. የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና

5. ትምህርት

6. ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)

7. ፀሎት

57. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 15፥18-27 **ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፡- ዓለም አንተን ይጠላል**

18. “**ዓለም ቢጠላችሁ፣ ከእናንተ በፊት እኔን እንደ ጠላኝ ዕወቁ።**

19. **እናንተ ከዓለም ብትሆኑ ኖሮ፣ ዓለም የራሱ እንደሆኑት አድርጎ በወደዳችሁ ነበር፤ ነገር ግን የዓለም ስላልሆናችሁና እኔ ከዓለም ለይቼ ስለ መረጥኋችሁ፣ ዓለም ይጠላችኋል።**

20. ‘**አገልጋይ ከጌታው አይበልጥም’ ብዬ የነገርኋችሁን ቃል አስታውሱ። እኔን አሳደውኝ ከሆነ፣ እናንተንም ያሳድዱአችኋል፤ እነርሱ ቃሌን ጠብቀው ከሆነም ቃላችሁን ይጠብቃሉ።**

21. **እነርሱ የላከኝን ስለማያውቁ በእኔ ምክንያት ይህን ሁሉ ያደርጉባችኋል።**

22. **እኔ መጥቼ ባልነግራቸው ኖሮ ኃጢአት ባልሆነባቸውም ነበር፤ አሁን ግን ለኃጢአታቸው ምክንያት የላቸውም።**

23. **እኔን የሚጠላ ሰው አባቴንም ይጠላል፤** 24. **ሌላ ሰው ያላደረገውን ሥራ በመካከላቸው ባላደርግ ኖሮ ኃጢአት ባልሆነባቸውም ነበር፤ አሁን ግን እነዚህን ታምራት አይተዋል፤ እኔንም አባቴንም ጠልተዋል።**

25. **ነገር ግን ይህም የሆነው፣ ‘ያለ ምክንያት ጠሉኝ’ ተብሎ በሕጋቸው የተጻፈው ቃል እንዲፈጸም ነው።**

26. “**እኔ ከአብ ለእነርሱ ዘንድ የምልክላችሁ፣ ከአብ የሚወጣው አጽናኙ የእውነት መንፈስ በመጣ ጊዜ፣ እርሱ ስለ እኔ ይመሰክራል።** 27. **እናንተም ደግሞ፣ ከመጀመሪያው ከእኔ ጋር ስለ ነበራችሁ፣ ትመሰክራላችሁ።**

**ቁ**. 18,22-25 **ዓለም ኢየሱስን ጠላ። ምክንያቱም ለዓለም ብርሃን የሆነው ኢየሱስ የጨለማውን ሥራ እየገለጸ ስለሚፈርድ ነው። ስለዚህ የዓለም ሰዎች ኢየሱስንና የሚያምኑ ሰዎችን ይጠሉአቸዋል።**

**ቁ**. 26,27 **መንፈስ ቅዱስ ለደቀ መዛሙርቱ የተሰጣቸው በዓለም ላይ ኢየሱስን እንዲመሰክሩ ነው። የዓለም ሰዎች የኢየሱስን ቃል ሰምተውና ድንቅ ምልክቶችንም አይተው እርሱን አያምኑም። ነገር ግን እግዚአብሔር መንፈስ ቅዱስ ስለ ኢየሱስ የመመስከርን ሥራ እንዳይቆም ያስቀጥላል። እኛ ወደ ዓለም ሄደን ኢየሱስን ስንመሰክር መንፈስ ቅዱስ ከእኛ ጋር ይሠራል።**

**ቁ**. 27 **በእኛ ውስጥ ያለው መንፈስ ቅዱስ ራሱ ሁሉ ጊዜ ስለ ኢየሱስ ስለሚመሰክር እኛም ደግሞ ኢየሱስን እንድንመሰክር ዘንድ በሕይወት እንኖራለን።**

**እንጸልይ፦ ጌታ ሆይ፤ እኛ ደግሞ የመንፈስ ቅዱስ ድምፅ ሰምተን ወደ ዓለምና ወደ ጐረቤቶቻችን ሄደን ኢየሱስን በመመስከር እንድንኖር እርዳን፤ አሜን**!

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ**? **ማን ነው**?

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ** (**በስራ ላይ ማዋል**)

7. **ፀሎት**

58. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 16፥1–15 **ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፡– የመንፈስ ቅዱስ ሥራ**

1. “**እኔ ይህን ሁሉ የነገርኋችሁ እመነታችሁ እንዳትሰናከሉ ነው።**

2. **ሰዎች እናንተን ከምኵራብ ያስወጧችኋል፤ እንዲያውም እናንተን የሚገድላችሁ ሁሉ እግዚአብሔርን የሚያገለግል የሚመስልበት ጊዜ ይመጣል።**

3. **እነርሱ ይህን ሁሉ የሚያደርጉባችሁ፣ አብን ወይም እኔን ስላላወቁ ነው።**

4. **ይህንን ለእናንተ የነገርኋችሁ ጊዜው ሲደርስ እንድታስታውሱ ነው፤ ከእናንተ ጋር ስለነበርሁ፣ ይህን ከመጀመሪያው አልነገርኋችሁም።**

5. “**አሁን ወደ ላከኝ እሄዳለሁ፤ ሆኖም ከእናንተ** ‘**ወዴት ትሄዳለህ?**’ **ብሎ የሚጠይቀኝ የለም።**

6. **ይህን ስለ ነገርኳችሁ ልባችሁ በሐዘን ተሞልቶአል፤**

7. **እኔ ግን በእውነት እላችኋለሁ፤ የእኔ መሄድ ለእናንተ ይሻላችኋል፤ እኔ ካልሄድኩ አጽናኙ ወደ እናንተ አይመጣም፤ እኔ ከሄድኩ ግን እርሱን ለእናንተ እልክላችኋለሁ።**

8. **እርሱ በመጣ ጊዜ ስለ ኃጢአት፣ ስለ ጽድቅና ስለ ፍርድም ዓለምን ይወቅሳል።**

9. **ስለ ኃጢአት የሚያጋልጠው ሰዎች በእኔ ስለማያምኑ ነው፤**

10. **ስለ ጽድቅ የሚያጋልጠው ወደ አብ ስለምሄድና ከእንግዲህ ስለማታዩኝ ነው፤**

11. **ስለ ፍርድ የሚያጋልጠው የዚህ ዓለም ገዢ ስለ ተፈረደበት ነው።**

12. “**ገና የምነግራችሁ ብዙ ነገር አለኝ፤ ነገር ግን አሁን ልትሸከሙት አትችሉም።**

13. **የእውነት መንፈስ በመጣ ጊዜ እናንተን ወደ እውነት ሁሉ ይመራችኋል። እርሱ ከራሱ አይናገርም፤ የሚሰማውን ብቻ ይናገራል፤ እንዲሁም ወደ ፊት ስለሚሆነው ይነግራችኋል፤**

14. **የእውነት መንፈስ የእኔ ከሆነው ወስዶ ለእናንተ ስለሚነግራችሁ እኔን ያከብረኛል።**

15. **የአብ የሆነው ሁሉ የእኔ ነው፤ የእውነት መንፈስ የእኔ ከሆነው ወስዶ ይነግራችኋል**’ **ያልኳችሁ ስለዚህ ነው።**

**ቁ.** 1,4 **ኢየሱስ ለደቀ መዛሙርቱ ቃሉን የተናገረው በችግሮቻቸው ጊዜ ይህን ቃል በማስታወስ በእምነት እንዲያሸንፉ ፈልጐ ነው። ኢየሱስ ከሄደ በኋላ ደቀ መዛሙርቱ በዓለም ጠላቶችን እንዲቀበሉ ነው። ስለዚህ ኢየሱስ በቃሉ ደቀ መዛሙርቶቹን አዘጋጀ።**

**ቁ.** 8−11 **መንፈስ ቅዱስ የዓለምን ኃጢአት ገለጸ። ኢየሱስ ለዓለም ኃጢአት በመስቀል ላይ ተሰቅሎ ሞተ። ነገር ግን አሁን መንፈስ ቅዱስ የዓለምን ኃጢአት የሚፈርድ ነው። መንፈስ ቅዱስ የዓለምን ኃጢአት ሲወቅስ ከኃጢአታቸው በንሰሓ ወደ ኢየሱስ የሚመለሱ ሰዎችን ሁሉ ይቅር ይላቸዋል። ደግሞም የመንፈስ ቅዱስን ስጦታ ይቀበላሉ።** (**ሐዋ.** 2፥37,38)

**ቁ.** 12−15 **በመንፈስ ቅዱስ ሥራ በኩል እግዚአብሔርና ኢየሱስ ክብርን ይቀበላሉ።**

**ቁ.** 5,6 **ደቀ መዛሙርቱም የኢየሱስን ቃል አላስተዋሉም። ምክንያቱም እነርሱ በኢየሱስ መሄድ ተጨንቀው ነበሩና። እኛም ቃሉን ሳናስተውል በልባችን ፈርተን ተጨንቀናልን**?

**እንጸልይ፦ ጌታ ሆይ፤ ወደ እኛ ችግሮቻችን ሲመጣ የኢየሱስን ቃል በልባችን ተቀብለን ችግሮቻችንን እንድናሸንፍ እርዳን፤ አሜን።**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

59. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 16፥16−24 **ወር፡** **ቀን፡**

**ርዕስ፡− የደስታ ጊዜ**

16. **"ከጥቂት ጊዜ በኋላ አታዩኝም፤ እንደገናም ከጥቂት ጊዜ በኋላ ታዩኛላችሁ።"**
17. **ከደቀ መዛሙርቱ አንዳንዶች፣ "ይህ፣ 'ከጥቂት ጊዜ በኋላ አታዩኝም፣ ደግሞ ከጥቂት ጊዜ በኋላ ታዩኛላችሁ፣ ደግመ ወደ አብ እሄዳለሁ' የሚለን ነገር ምንድን ነው?" ተባባሉ።**
18. **"እንግዲህ ይህ 'ከጥቂት ጊዜ በኋላ' የሚለው ነገር ምንድን ነው? የሚናገረውን ነገር አናውቅም" እያሉ ይጠያየቁ ነበር።**
19. **ኢየሱስም ሊጠይቁት እንደ ፈለጉ አውቆ እንዲህ አላቸው፣ "እርስ በርሳችሁ የምትጠያየቁ፣ 'ከጥቂት ጊዜ በኋላ አታዩኝም፣ ደግሞም በጥቂት ጊዜ በኋላ ታዩኛላችሁ' ምን ማለቴ እንደ ሆነ እርስ በርሳችሁ ትጠያየቃላችሁ?**
20. **እኔ በእውነት እላችኋለሁ፣ እናንተ ታለቅሳላችሁ፣ ትጮኻላችሁም፣ ዓለም ግን ደስ ይለዋል፤ እናንተ ታዝናላችሁ፣ ነገር ግን ሐዘናችሁ ወደ ደስታ ይለወጣል።**
21. **ሴት በምትወልድበት ጊዜ የምጥ ቀንዋ ስለ ደረሰ ታዝናለች፣ ከወለደች በኋላ ግን በዓለም ላይ ሕፃን ስለ ተወለደ ከመደሰትዋ የተነሣ ጭንቀትዋን አታስታውሰውም።**
22. **እንዲሁም እናንተ አሁን ታዝናላችሁ፣ ነገር ግን እኔ እንደገና አያችኋለሁ፣ ልባችሁም ደስ ይለዋል፤ ደስታችሁንም የሚወስድባችሁ የለም።**
23. **በዚያ ቀን ከእኔ ምንም አትለምኑም፣ በእውነት እላችኋለሁ እናንተ አብን በስሜ የምትለምኑትን ሁሉ ይሰጣችኋል።**
24. **እስከ አሁን እናንተ በስሜ ምንም ነገር አለመናችሁም፣ ለምኑ ይሰጣችኋል፣ ደስታችሁም ፍጹም ይሆናል።**

**ቁ.** 16−19 **ኢየሱስ የመዳንን ሥራ ከደቀ መዛሙርቱ ጋር እንዳደረገ ገለጸ። አሁን እኛ የኢየሱስ ቅባት አልተለማመድንም። ነገር ግን በመንፈስ ቅዱስ በኩል የኢየሱስ ቅባት ልንለማመድ እንችላለን። ዛሬ እኛ በቃልና በጸሎት በእኛ ውስጥ የሚኖረውን ጌታ እንለማመዳለን።**

**ቁ**. 20−22 ኢየሱስ አዲስ የደስታ ጊዜ ስለመምጫው ነገራቸው። የኢየሱስ በመስቀል ላይ መሞት ለደቀ መዛሙርቱ ታላቅ ሐዘን ሲሆን፣ ነገር ግን የትንሣኤውን ብርሃን ሲያዩ ያ ሐዘናቸው ወደ ደስታ ተመልሷል።

**ለምሳሌ፦** ሕፃን በሚወለድበት ጊዜ የሕፃኑ እናት በስቃይ ከወለደች በኋላ ሕፃኑን ስታይ ሚጡ ሁሉ ተረስቶ ታላቅ ደስታ ይሰማታል። እንደዚሁም ኢየሱስ ስለ እኛ በመስቀል ላይ ተሰቅሎ ከሞተ በኋላ በትንሣኤ ድልና በመንፈስ ቅዱስ ቅባት በኩል በአዲስ ደስታ ይደሰታል።

**ቁ**.17,18 ደቀ መዛሙርቱ የኢየሱስን ቃል ብዙ ጊዜ ሰምተዋል። ነገር ግን አላስተዋሉም። ለእኛ ደግሞ ኢየሱስ እንደ ገና የሰጠው ቃል ምንድን ነው? እኛ እንደ ደቀ መዛሙርት እንዳንደናበር መንፈስ ቅዱስ ማስተዋል እንዲሰጠን እንጸልያለን።

**ቁ**. 23,24 መንፈስ ቅዱስ በመምጣቱ በኩል ኢየሱስ በደቀ መዛሙርቱ ውስጥ የሚኖረው አዲስ ጊዜ በኢየሱስ ስም የሚጸልዩበት ጊዜ ነው። የጸሎት ርዕሶች አይወሰንም። በኢየሱስ ስም በመመካት ወደ እግዚአብሔር ማንኛውንም ነገር ስንጸልይ በደስታ ይመልሰናል።

**እንጸልይ፦** ጌታ ሆይ፣ ሁልጊዜ በኢየሱስ ስም ማንኛውንም ነገር እንድንጠይቅ እርዳን፣ አሜን!

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

60. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 16፥25−33 **ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፦ እኔ ዓለምን አሸነፍኩ**

25. **እስከ አሁን እኔ በምሳሌ ነገርኳችሁ፤ ከእንግዲህ ግን ስለ አብ በምሳሌ ሳይሆን በግልጽ የምናገርበት ጊዜ ይመጣል።**

26. **በዚያ ቀን በስሜ ትለምናላችሁ፤ ይህም በእናንተ ፈንታ አብን እለምናለሁ ማለቴ አይደለም፤**

27. **እናንተ እኔን ስለ ወደዳችሁኝና ከእግዚአብሔርም እንደ ወጣሁ ስላመናችሁ አብ እናንተን ራሱ ይወዳችኋል።**

28. **እኔ ከአብ ወጥቼ ወደ ዓለም መጥቻለሁ፤ እንደገናም ይህን ዓለም ትቼ፤ ወደ አብ እሄዳለሁ።"**

29. **ከዚያም ደቀ መዛሙርቱ እንዲህ አሉ፤ "አሁን በምሳሌ ሳይሆን በግልጥ ተናገርክ፤**
30. **አሁን ሁሉን ነገር እንደምታውቅና ማንም ሊጠይቅህ እንደማያስፈልግ ተረድተናል፤ ይህም ከእግዚአብሔር እንደ ወጣህ እናምናለን።"** 31. **ኢየሱስ እንዲህ ሲል መለሰላቸው፤ "አሁንስ አምናችኋል?**

32. **እነሆ፤ ሁላችሁም ወደ ቤት የምትበታተኑበት ጊዜ ይመጣል፤ ያም ጊዜ አሁን ነው። እናንተ እኔን ብቻዬን ትተዉኛላችሁ፤ ነገር ግን አብ ከእኔ ጋር ስለ ሆነ ብቻዬን አይደለሁም።** 33. **ይህን ለእናንተ መናገሬ በእኔ ሰላም እንዲኖራችሁ፤ እናንተ በዓለም ሳላችሁ መከራ አለባችሁ፤ ነገር ግን አይዞአችሁ፤ እኔ ዓለምን አሸንፌዋለሁ።"**

**ቁ.** 25 **በመስቀል ላይ ሞትን ድል አድርጐ የተነሣው ኢየሱስ በመንፈስ ቅዱስ በኩል በመጨረሻ ሁሉን ነገር ገለጸ። አዲስ ጊዜው መንፈስ ቅዱስ ሁሉንም በእውነት የሚመራበት ጊዜ ነው።** (13) **አሁን በምሳሌ የሚነገርበት ጊዜ አይደለም። ኢየሱስ ዛሬ እኛ በመንፈስ ቅዱስ ውስጥ እውነትን እንድንረዳ ከሕይወታችን ብዙ ደስታን እንድንካፈል ይፈልጋል።**

**ቁ.** 32 **ደቀ መዛሙርቱ ሁሉ ኢየሱስን ትተው ሲወጡ እግዚአብሔር ከኢየሱስ ጋር ነው። ኢየሱስ ብቻውን ሲሆን በእግዚአብሔር ዓይኖች ፊት የመሆኑ ስሜት ሲሰማው በሠላም ይደሰታል። በምንም ዓይነት ሁኔታ ከቶ የማይተወውን እግዚአብሔርን ይታመናል።** (**ዕብ፡**13፥15)

**ቁ**. 33 ኢየሱስ እንደገና ለእነርሱ ዓለም የማይወስደውን ሠላም በድፍረት እንዲከፋፈሉ የሠላምን ተስፋ ሰጣቸው። ኢየሱስ ይህን ታላቅ ስጦታን ለመስጠት በመስቀል ላይ ሞተና ከሦስት ቀን በኋላ ተነሥቶ ክፋትን ሁሉ አሸነፈ። አሁን በምንም ዓይነት ችግር የተጨነቀ አለ? አይዞአችሁ! ኢየሱስ ዓለምን የሚያሸንፍ ሠላምን ይሰጣችኋል።

**ቁ**. 26-28 አዲስ ጊዜው የኢየሱስ ደቀ መዛሙርት በኢየሱስ ስም ወደ እግዚአብሔር የሚጸልዩበት ጊዜ ነው። ኢየሱስ እኛ በፀጋው ዙፋን ፊት ቀርበን ሁልጊዜ ወደ እግዚአብሔር እንድንጸልይ የሕይወትን መንገድ ከፈተልን። (ዕብ፡ 4፥16)

**እንጸልይ፡- ጌታ ሆይ፤ አሁን ለእኛ ችግሮቻችን ቢኖሩም ወደ እግዚአብሔር ጸልየን ችግሮቻችንን እንድናሸንፍ እርዳን፤ አሜን!**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

61. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 17፥1-8 **ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፡- ኢየሱስ ስለ ራሱ ጸለየ**

1. **ኢየሱስ ይህን ከተናገረ በኋላ፣ ወደ ሰማይ ቀና ብሎ እንዲህ ሲል ጸለየ፣ "አባት ሆይ፣ ጊዜው ደርሶአል፣ ልጅህ ያከብርህ ዘንድ ልጅህን አክብረው፣**

2. **ከአንተ ለተቀበላቸው ሁሉ የዘላለምን ሕይወት እንዲሰጥ በሰው ሁሉ ላይ ለልጅ ሥልጣንን ሰጥተኸዋልና።**

3. **የዘለዓለም ሕይወትም አንተ ብቻ እውነተኛውን አምላክና የላክኸውን ኢየሱስ ክርስቶስን ማወቅ ነው።**

4. **እኔ ከአንተ የሰጠኸኝን ሥራ ፈጽሜ በምድር ላይ አከበርኩህ።**

5. **አባት ሆይ**! **ዓለም ከመፈጠሩ በፊት ከአንተ ጋር በነበረኝ ክብር አሁንም በአንተ ዘንድ አክብረኝ።**

6. "**እኔ ከዓለም ውስጥ መርጠህ ለሰጠኸኝ ሰዎች ስምህን ገለጥኩላቸው፣ እነርሱ የአንተ ነበሩ፣ አንተ እነርሱን ለእኔ ሰጠኸኝ፣ እነርሱም ቃልህን ጠብቀዋል፣**

7. **እነርሱን የሰጠኸኝ ሁሉ ከአንተ እንደ ሆነ አሁን አውቀዋል፣**

8. **እኔ ከአንተ የሰጠኸኝን ቃል ሰጥቻቸዋለሁ፣ እነርሱም ቃሉን ተቀብለውታል፣ እኔም ከአንተ እንደ ወጣሁ በርግጥ አውቀዋል፣ አንተ እኔን እንደ ላክኸኝም አምነዋል፣**

**ቁ**. 1,5 **ኢየሱስ እንደ አንድ ዘር ሞቶ ለእግዚአብሔር ክብርን ሰጠ።** (**ዮሐ**፡12፥23-28)

**ቁ**. 2,4 **እግዚአብሔር ለሁሉም ሰዎች የዘላለምን ሕይወት እንዲሰጣቸው ሥልጣኑን ለኢየሱስ ሰጠ።**

**ቁ**. 3 **የዘላለም ሕይወት እውነተኛ ምንጭ ኢየሱስንና እግዚአብሔርን ማወቅ ነው። የዘላለም ሕይወት ማለት እግዚአብሔርንና ኢየሱስ በማወቅ የግል አዳኝ አድርጐ አምኖ የመታዘዝ ልምምድ ነው።**

**ቁ**. 6-8 **ደቀ መዛሙርቱም በኢየሱስ ቃል በኩል ራሳቸው ከእግዚአብሔር ኢየሱስ እንደ መጣ አውቀው ቃሉን እንዲጠብቁ ሙሉ እምነት ሆነላቸው። እኛ የክርስቶስ ደቀ መዛሙርቶች ነን**?

**እንጸልይ፡-** **ጌታ ሆይ፣ እኛ ሁሉ ጊዜ ቃልህን እንድንታዘዝና አምነንም እንድንከተል እርዳን፣ አሜን**!

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

62. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 17፥9—19 **ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፡— ኢየሱስ ስለ ደቀ መዛሙርቱ ጸለየ**

9. **"እኔ ለእነርሱ እጸልያለሁ፣ አንተ ለእኔ የሰጠኸኝ የአንተ ስለ ሆኑ ለእነርሱ እጸልያለሁ፣ ለዓለም አልጸልይም።**

10. **የእኔ የሆነው ሁሉ የአንተ ነው የአንተም የሆነው የእኔ ነው፣ እኔም በእነርሱ እከብራለሁ።**

11. **እኔ ከእንግዲህ ወዲህ በዓለም ላይ አልኖርም፣ እነርሱ ግን በዓለም ናቸው። እኔ ወደ አንተ መምጣቴ ነው፣ ቅዱስ አባት ሆይ፣ አንተ የሰጠኸኝ እንደእኛ አንድ እንዲሆኑ ለእኔ በሰጠኸኝ ስምህ ጠበቃቸው።**

12. **እኔ አብሬአቸው በነበርኩ ጊዜ አንተ ለእኔ በሰጠኸኝ ስምህ ጠብቄአቸዋለሁ፣ እኔ ጠበቅኋቸው፣ የቅዱስ መጽሐፍ ቃል እንዲፈጸም ከዚያ ከጥፋት ልጅ በቀር ከቶ ከእነርሱ ማንም አልጠፋም።**

13. **አሁን እኔ ወደ አንተ መምጣቴ ነው፣ በዓለም ላይ ሳለሁ ይህን የምናገረው ደስታዬ በእነርሱ ዘንድ ፍጹም እንዲሆን ነው።** 14. **እኔ ቃልህን ለእነርሱ ሰጥቻቸዋለሁ፣ እኔ ከዓለም እንዳይደለሁ እነርሱም ከዓለም አይደሉም፣ ስለዚህ ዓለም ጠላቸው።**

15. **እኔ ለአንተ የምለምንህ ከክፉው እነርሱን እንድትጠብቃቸው እንጂ፣ ከዓለም እንድታወጣቸው አይደለም።**

16. **እኔ ከዓለም እንዳይደለሁ እነርሱም ከዓለም አይደሉም።**

17. **በእውነትህ እነርሱን ቀድሳቸው፣ ቃልህ እውነት ነው።**

18. **አንተ እኔን ወደ ዓለም እንደ ላክኸኝ እኔም እነርሱን ወደ ዓለም ላክኋቸው።**

19. **እነርሱ በእውነት ቅዱሳን እንዲሆኑ እኔ ራሴን ስለ እነርሱ ቅዱስ አደርጋለሁ።**

**ቁ.** 9,10 **ኢየሱስ ከመሞቱ በፊት ለደቀ መዛሙርቱ እስከ መጨረሻ ድረስ ጸለየ። ስለዚህ እነርሱ የእግዚአብሔር ንብረትና ጌታን ለማክበር የተሰጡ ሰዎች ናቸው።**

**ቁ**. 11,12 ኢየሱስ በዓለም ላይ የሚቆዩትን ደቀ መዛሙርቱን እንደ እኛ ጠብቃቸው ብሎ ወደ አባቱ ጸለየ። ስለዚህ እግዚአብሔርና እርሱ አንድ እንደ ሆኑ ደቀ መዛሙርቶቹም አንድ ይሆኑ ዘንድ ይፈልጋል። ዛሬ እኛ በዓለም እንድንጠበቅ የተቀበልነውን አንድ የሚያደርግ ብቸኛ መንገዱን በእግዚአብሔር ስምና በቃሉ ውስጥ መኖር ነው። (ቁጥ፡6−8)

**ቁ**. 14−16 ኢየሱስ በዓለም ላይ ደቀ መዛሙርቶቹ እንዲጠበቁ ጸለየ። ዓለም ኢየሱስን እንደ ጠላ ደቀ መዛሙርቶችን ይጠላቸዋል። ነገር ግን እግዚአብሔር ኢየሱስን እንደ ጠበቀ ደቀ መዛሙርቶችንም እንደሚጠብቃቸው እኛንም ይጠብቀናል።

**ቁ**. 17−19 ኢየሱስ ደቀ መዛሙርቱን በእውነት እንዲቀደሱ ጸለየ። እርሱ በቅድስና ሕይወት ለአባቱ እንደታዘዘ እኛም በቅድስና ሕይወት እንድንከተልም ለእኛ ጥሩ ምሳሌ ሆኗልናል።

**እንጸልይ፦ ጌታ ሆይ፤ እኛን ከዓለም እንድትጠብቅና እንደ ኢየሱስ በቅድስና ሕይወት እንድንታዘዝ እርዳን፤ አሜን!**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

63. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 17፥20−26 **ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፡− ኢየሱስ ለሁሉ ምዕመናን ሰዎች ጸለየ**

20. “**የእነርሱን ቃል ተቀብለው በእኔ ለሚያምኑ እጸልያለሁ፤ እኔ ለእነርሱ ብቻ አልጸልይም፤**

21. **አባት ሆይ!** **አንተ በእኔ እንዳለህ፤ እኔም በአንተ እንዳለሁ፣ የምለምነው ሁሉም አንድ እንዲሆኑ ነው፣ እነርሱም በእኛ እንዲኖሩ ነው፣ አንተ እንደ ላክኸኝም ዓለም እንዲያምን ነው።**

22. **እኛ አንድ እንደ ሆንን እነርሱም አንድ እንዲሆኑ ለእኔ የሰጠኸኝን ክብር ሰጥቻቸዋለሁ።**

23. **ይህም እኔ በእነርሱ፣ አንተም በእኔ መሆንህ ነው፣ እነርሱም በፍጹም አንድ እንዲሆኑ ነው፣ እንዲሁም አንተ እኔን እንደ ላክኸኝና እኔን በወደድከኝ መጠን እነርሱንም እንደ ወደድካቸው ዓለም እንዲያውቅ ነው።**

24. **አባት ሆይ፣ እነዚህ የሰጠኸኝ፣ እኔ ባለሁበት እንዲሆኑ ዓለም ሳይፈጠር ስለ ወደድኸኝ የሰጠኸኝንም ክብሬን እንዲያዩ እፈልጋለሁ።**

25. **ጻድቅ አባት ሆይ፣ ዓለም አንተን ባያውቅህም፣ እኔ አወቅሃለሁ፣ እነዚህም አንተ እኔን እንደ ላከኸኝ ያውቃሉ።**

26. **አንተ እኔን የወደድክበት ፍቅር በእነርሱ ላይ እንዲሆንና እኔም በእነርሱ እንድሆን እነርሱ አንተን እንዲያውቁ አድርጌአለሁ፣ ደግሞም እንዲያውቁ አደርጋቸዋለሁ።**”

**ቁ.** 20 **ኢየሱስ ስለ ደቀ መዛሙርቱ ሕይወትና ሥራ እንዲሁም ወደ ፊት ለሚያምኑ ለሌሎች ደቀ መዛሙርቶች ጸለየ።**

**ቁ.** 21−23 **ኢየሱስ ሁሉ ክርስቲያን አንድ እንዲሆኑ ይፈልጋል። እግዚአብሔር በኢየሱስ ውስጥ እንዳለ እንዲሁም በኢየሱስ ውስጥ እግዚአብሔር አለ። እኛም ደግሞ በኢየሱስ ውስጥ ስንኖር እውነቱ አንድ ይሆናል።**

**ቁ.** 24 **እግዚአብሔር በኢየሱስ ውስጥ እንዳለ ደግሞ እኛ ከኢየሱስ ጋር እንድንኖር ይፈልጋል። ስለዚህ ኢየሱስ ያለበት ቦታ የክብር ቦታ ነው። ያ ቦታ**

**እግዚአብሔር የሚኖርበት የክብር ቦታ ነው። ዛሬ ኢየሱስ የሚኖርበት ቦታ የትኛው ነው**? **ይህ ኢየሱስ በእኛ ውስጥ አለ**?

**ቁ**. 25,26 **ኢየሱስ ለደቀ መዛሙርቱ የእግዚአብሔርን ሥምና ፈቃዱን አውቀው እንዲኖሩ ሥልጣን ሰጣቸው።**

**እንጸልይ፦ ጌታ ሆይ፤ በኢየሱስ እየተደሰትን የእግዚአብሔር ፍቅር እንድንለማመድ እርዳን፤ አሜን**!

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ**? **ማን ነው**?

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ** (**በስራ ላይ ማዋል**)

7. **ፀሎት**

64. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 18፥1–11 **ወር፡** **ቀን፡**

**ርዕስ፡– የኢየሱስ ሥልጣን**

1. **ኢየሱስ ይህን ካለ በኋላ ከደቀ መዛሙርቱ ጋር ወደ ቄድሮን ሸለቆ ማዶ ሄደ፣ እዚያ ወደ ነበረውም የአትክልት ስፍራ ከደቀ መዛሙርቱ ጋር ገቡ።**

2. **ብዙውን ጊዜ ኢየሱስ ከደቀ መዛሙርቱ ጋር በዚያ ይሰበሰቡ ስለ ነበር፣ አሳልፎ የሰጠው ይሁዳም ቦታውን ያውቅ ነበር።** 3. **ስለዚህ ይሁዳ አንድ የወታደሮች ጭፍራ፣ እንዲሁም ከካህናት አለቆችና ከፈሪሳውያን የተላኩ ሎሌዎችን እየመራ ወደ አትክልቱ ስፍራ መጣ፣ እነርሱም ችቦ፣ ፋኖስና የጦር መሣሪያ ይዘው ነበር።**

4. **ኢየሱስም የሚደርስበትን ሁሉ አውቆ ወደ እነርሱ ወጣ ብሎ “ማንን ትፈልጋላችሁ?” አላቸው።**

5. **እነርሱም “የናዝሬቱን ኢየሱስ እንፈልጋለን” አሉት። ኢየሱስም፣ “እርሱ እኔ ነኝ” አላቸው። አሳልፎ የሰጠው ይሁዳም ከእነርሱ ጋር ቆሞ ነበር።**

6. **ኢየሱስም፣ “እርሱ እኔ ነኝ” ባለ ጊዜ ወደ ኋላ አፈግፍገው መሬት ላይ ወደቁ።**

7. **ኢየሱስም “ማንን ትፈልጋላችሁ?” ሲል እንደገና ጠየቃቸው። እነርሱም “የናዝሬቱን ኢየሱስ እንፈልጋለን” አሉ።**

8. **ኢየሱስም መልሶ፣ “ ‘እርሱ እኔ ነኝ’ ብያችኋለሁ እኮ፣ እናንተ እኔን የምትፈልጉ ከሆነ፣ እነዚህ ይሂዱ፣ ተዉአቸው” አለ፣** 9. **ይህም የሆነው፣ “አባት ለእኔ ከሰጠኸኝ ሰዎች አንዱን እንኳ አላጠፋሁም” ብሎ የተናገረው ቃል እንዲፈጸም ነው።** 10. **ሰይፍ ይዞ የነበረውም ስምዖን ጴጥሮስም ሰይፉን መዘዘ፣ የካህናት አለቃውን አገልጋይ መትቶ ቀኝ ጆሮውን ቈረጠ፤ የአገልጋዩም ስም ማልኮስ ይባል ነበር።**

11. **ኢየሱስም ጴጥሮስን፣ “ሰይፍህን ወደ ሰገባው ክተተው፤ አብ የሰጠኝን ጽዋ አልጠጣምን?” አለው።**

**ቁ.** 4–8 **ኢየሱስ እርሱን ለመያዝ ለመጡ ሰዎች የእግዚአብሔርን ሥልጣን በትክክል ገለጸ። የክብር እግዚአብሔር ሲገልጽ ኢየሱስን የሚይዙ ሰዎች ፈርተው በምድር ላይ ወደቁ። ኢየሱስ ክፋትን ይዞ ለማሸነፍ አይደለም። ኢየሱስ ለእግዚአብሔር ፍቃድ የታዘዘው እኛን ለማዳን ነው።**

**ቁ.** 3 **የአስቆሮንቱ ይሁዳ ኢየሱስ የሰጠውን ልዩ መብትና የቀረጥ ሥልጣን አልፈልግም ብሎ ወጣ። ነገር ግን እርሱ ዓለም የሚሰጠው ገንዘብን፣ ተቀብሎ ጦር ሠራዊትን ይዞ ኢየሱስን ለመያዝ መጣ። እኛ ጌታ በሚሰጠው የመንፈሳዊ ልዩ መብትና ሥጦታ እንዲሁም ሹመት በአስተሳሰባችን ትክክል ነን? ወይም ዓለም በሚሰጠው ዕቃዎችና ክብር ሥልጣንና ጤናን ይበልጥ ስናስብ ትክክል ነን?**

**ቁ.** 6 **የዓለም ሥልጣን ኢየሱስን መጥላት ሲሆን የጌታ ቃል ሥልጣን ግን የዓለም ሰዎችን በምድር ላይ ይጥላቸዋል። ዓለምን አትፍራ! የመንፈስ ቅዱስ ሥልጣን ያስፈልግሃል።**

**ቁ.** 10,11 **ኢየሱስ ወደ ሞት መንገድ ሲሄድ ደቀ መዛሙርቱን ጠበቃቸው። ነገር ግን ጴጥሮስን የዓለም ስሥልጣን ስላደረገ አወዳደረ። እኛ እንዴት የእግዚአብሔርን መንግሥት እንጠብቃለን? በተሳሳተ ስሜት የእግዚአብሔርን መንግሥት ሥራ አቋረጥን?**

**እንጸልይ፡– ጌታ ሆይ፤ እኛ እንደ እግዚአብሔር ቃል እንደ ፈቃዱ እንድንኖር እርዳን፤ አሜን!**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

**ርዕስ፡- ታላቁ ንጉሥና ቦቅቧቃ ደቀ መዝሙር**

12. **ከዚህ በኋላ ወታደሮቹና አዛዦቻቸው፣ የአይሁድ የዘብ ሎሌዎች ኢየሱስን ይዘው አሰሩት።**

13. **በመጀመሪያ ወደ ሐና ወሰዱት፤ ሐና በዚያ ዓመት የካህናት አለቃ ለነበረው ለቀያፋ ዐማቱ ነበር።**

14. **ቀያፋ "አንድ ሰው ስለ ሕዝቡ ቢሞት የተሻለ ነው" ብሎ አይሁድን የመከረ ነበር።**

15. **ስምዖን ጴጥሮስና ሌላው ደቀ መዝሙር ኢየሱስን ተከተሉት፤ ያ ሌላው ደቀ መዝሙር በካህናት አለቃው ዘንድ የታወቀ ነበር፤ ስለዚህ ከኢየሱስ ጋር ወደ ካህናት አለቃው ግቢ ገባ፤**

16. **ጴጥሮስ ግን በውጭ በበሩ አጠገብ ቀረ፤ በካህናት አለቃው የታወቀው ደቀ መዝሙር ተመልሰና በር ለበረኛይቱ ልጃገረድ ነግሮ ጴጥሮስን ይዞት ገባ።**

17. **በረኛይቱም ልጃገረድ ጴጥሮስን "አንተም ከዚህ ሰው ደቀ መዛሙርት አንዱ አይደለህምን?" አለችው። እርሱም፣ "አይደለሁም" አለ።**

18. **ጊዜው ብርድ ስለ ነበረ አገልጋዮቹና ሎሌዎቹ ባያያዙት የከሰል እሳት አንድደው ቆመው ይሞቁ ነበር፤ ጴጥሮስም ከእነርሱ ጋር ቆሞ እሳት ይሞቅ ነበር።**

19. **በዚያን ጊዜ የካህናት አለቃው ኢየሱስን ስለ ደቀ መዛሙርቱና ስለ ትምህርቱ ጠየቀው።**

20. **ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰለት፤ "እኔ ለሰው ሁሉ በግልጥ ተናገርኩ፤ አይሁድ ሁሉ በሚሰበሰቡበት በምኵራብም ሆነ በቤተ መቅደስ፣ ዘወትር አስተማርኩ፤ በስውር የተናገርኩት ምንም ነገር የለም፤**

21. **ታዲያ፣ ለምን እኔን ትጠይቀኛለህ? ስናገራቸው የሰሙኝን ጠይቃቸው፤ የተናገርኩትን እነርሱ ያውቃሉ።"**

22. **ኢየሱስ ይህን በተናገረ ጊዜ እዚያ ቆመው ከነበሩት ከነበሩት ሎሌዎች አንዱ፣ "ለካህናት አለቃው የምትመልሰው እንዲህ ነውን?" ብሎ ኢየሱስን በጥፊ መታው።**

23. **ኢየሱስም፣ "ክፉ ቃል ተናግሬ ከሆነ ክፉ መናገሬን መስክር፤ የተናገርኩት ትክክል ከሆነ ግን ለምን ትመታኛለህ?" አለው።**

24. ከዚህ በኋላ ሐና፣ ኢየሱስን እንደ ታሰረ ወደ ካህናት አለቃው ወደ ቀያፋ ላከው።
25. ስምዖን ጴጥሮስ ቆሞ እሳት ይሞቅ ነበር፤ የዚያን ጊዜ ሌሎች ሰዎችም፣ "አንተ ከኢየሱስ ደቀ መዛሙርት አንዱ አይደለህምን?" አሉት፡ ጴጥሮስም፣ "አይደለሁም!" ብሎ ካደ።
26. ጴጥሮስ ጆሮውን የቈረጠው ሰው ዘመዱ የሆነው ከካህናት አለቃው ሎሌዎች አንዱ፣ "በአትክልቱ ስፍራ አንተን ከኢየሱስ ጋር አላየሁህም?" ሲል ጠየቀው።
27. ጴጥሮስም እንደገና ካደ፤ ወዲያውኑ ዶሮ ጮኸ።

**ቁ**. 19−23 ኢየሱስ በከፍተኛ ካህናት ፊት በድፍረት መለሰ። በዚህ መልስ ምክንያት ቤተ መቅደሱን የሚጠብቅ ዘበኛ ኢየሱስን መታ። ነገር ግን ኢየሱስ አለመታዘዝንና አለመግባባትን አስወገደ። ይህ ጌታ ዛሬም ከእኛ ጋር አለ። የዓለም ፈተና፣ ክብደትና ግፍያ ሲመጣ ወደ ኋላ አልሸሸም።

**ቁ**. 12,13 የሃይማኖት መሪዎች ኢየሱስን ያዙት። ነገር ግን ለእነርሱ ኢየሱስን የሚያዩበት መንፈሳዊ ዓይን የላቸውም። እኛ ደግሞ እንደዚህ እዳናደርግ እንጠንቀቅ።

**ቁ**. 15,18 ኢየሱስ በታላቅ ባለሥልጣኖች ፊት በድፍረት መለሰ። ነገር ግን ጴጥሮስ ሦስት ጊዜ ኢየሱስን ካደ። እኛ ደግሞ እምነታችንን ስንገልጽ እንደ ቦቅባቃ ደቀ መዝሙር ነን?

**ቁ**. 25,27 ጴጥሮስ የኢየሱስ ደቀ መዛሙር መሆኑን ካደ። ኢየሱስ ከሰዎች ጋር እሳት የሚሞቀውን ጴጥሮስን ተመለከተ። እኛም ደግሞ ከክርስቲያኖች ተሸሽገን ከዓለም ሰዎች ጋር እሳትን እየሞቅን ነን?

**እንጸልይ፡- ጌታ ሆይ፤ ወደ እኛ ከሚመጡ መከራና ፈተናዎች ይልቅ የጌታን ሥልጣን አተልቀን ማየት እንድንችል እርዳን፤ አሜን!**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

66. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 18፥28−38 **ወር፡** **ቀን፡**

**ርዕስ፡− የመንግሥት ሰማይ ንጉሥ ፈተና**

28. **ከዚህ በኋላ አይሁድም ኢየሱስን ከቀያፋ ወደ ሮማዊው ገዢ ግቢ ይዘውት ሄዱ፤ ጊዜውም ጠዋት ማለዳ ነበር፤ አይሁድ ለፋሲካ በዓል የሚታረደውን በግ መብላት ስለ ነበረባቸው እንዳይረክሱ በማለት ወደ አገረ ገዢው ግቢ ውስጥ አልገቡም።** 29. **ስለዚህ ጲላጦስ ወደ እነርሱ ወጥቶ፣ "ይህን ሰው ስለ ምን ትከሱታላችሁ" ሲል ጠየቃቸው።** 30. **እነርሱም፣ "ይህ ሰው ክፉ አድራጊ ባይሆን ኖሮ ለአንተ አሳልፈን ባልሰጠነውም ነበር" ብለው መለሱለት።**

31. **ጲላጦስም፣ "እናንተ ራሳችሁ ወስዳችሁ በሕጋችሁ መሠረት ፍረዱበት!" አላቸው። አይሁድም "እኛ ሰውን ለመግደል መብት የለንም" አሉት።** 32. **ይህም የሆነው ኢየሱስ በምን ዓይነት ሞት እንደሚሞት የተናገረው ቃል እንዲፈጸም ነው።** 33. **ጲላጦስም እንደገና ወደ ገዥ ግቢ ገባና ኢየሱስን ጠርቶ፣ "አንተ የአይሁድ ንጉሥ ነህን?" ብሎ ጠየቀው።** 34. **ኢየሱስ፣ "አንተ ይህን የምትለው ከራስህ ነውን? ወይስ ሌሎች ይህን ስለ እኔ የነገሩህ?" ሲል መለሰለት።** 35. **ጲላጦስም መልሶ፣ "እኔ አይሁዳዊ ነኝን? አንተን ለእኔ አሳልፈው የሰጡህ ወገኖችህና የካህናት አለቆች ናቸው፤ ለመሆኑ ምን አድርገህ ነው?" አለው።** 36. **ኢየሱስ፣ "የእኔ መንግሥት ከዚህ ዓለም አይደለችም፤ መንግሥቴ ከዚህ ዓለም ብትሆን ኖሮ አይሁድ እንዳይዙኝ ሎሌዎቼ በተከላከሉልኝ ነበር፣ መንግሥቴ ግን ከዚህ ዓለም አይደለችም" ሲል መለሰ።** 37. **ጲላጦስም፣ "ታዲያ፣ አንተ ንጉሥ ነኻ?" አለው። ኢየሱስም፣ "እኔ ንጉሥ እንደ ሆንኩ አንተ ትላለህ፤ እኔ የተወለድኩትና ወደ ዓለም የመጣሁት ስለ እውነት ልመሰክር ነው፤ ከእውነት የሆነ ሁሉ ቃሌን ይሰማል" ሲል መለሰ።** 38. **ጲላጦስም፣ "እውነት ምንድን ነው?" ብሎ ጠየቀ። ከዚህ በኋላ ጲላጦስ እንደገና ወደ አይሁድ ወጥቶ እንዲህ አላቸው፣ "እኔ ምንም በደል አላገኘሁበትም፤**

**ቁ.** 28−32 **በዓለም ክፉ መሪዎች መካከል ተይዞ እንደሚቆይ ያያል። ነገር ግን ይህ እግዚአብሔር አስቀድሞ ኢየሱስን በመስቀል ላይ እንዲሞት በእኛቸው አሳልፎ ሊሰጥ ወስኗል። እኛንም ለማዳን እግዚአብሔር ኢየሱስን ለክፉ ሰዎች አሳልፎ ሰጠ።**
**ቁ.** 33−38 **ኢየሱስን "አንተ የአይሁድ ንጉሥ ነህ" ብሎ ጳላጦስ ጠየቀው። ኢየሱስም መልሶ የዚህ ዓለም መንግሥት ንጉሥ አይደለሁም። የእግዚአብሔር**

መንግሥት እውነተኛ ንጉሥ ነኝ። ኢየሱስ ንጉሥ ሆኖ የመንግሥትን ሥልጣን ለመጠቀም አይፈልግም። ነገር ግን በእውነት ውስጥ የሚደረግ መንግሥት ነው። እኛ የምንፈልገው የትኛውን መንግሥት ነው?

**ቁ.** 28 አይሁድ ከፋሲካ በዓል ፊት ሰውነታቸውን ያላነጹ የውጭ አገር ሰዎች ወደ ፋሲካ በዓሉ ቦታ አያስገቡም። እንደዚህ በማድረግ ቅድስናቸውን ለመጠበቅ ይሞክራሉ። ነገር ግን እውነተኛ የፋሲካ ጠቦት የሆነው ኢየሱስ ሰዎችን ከርኩሰት ለማንጻት ሞተ። እኛ ትእዛዞችን እየጠበቅን አዛዡ የሆነው ጌታ ኢየሱስ ከወደደው ሥራ ርቀናልን?

**እንጸልይ፡**– ጌታ ሆይ፣ በኢየሱስ በኩል እውነተኛ መንግሥትን ለእኛ ስለሰጠህ እናመሰግናለን፣ አሜን!

1. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ

2. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት

3. እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?

4. የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና

5. ትምህርት

6. ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)

7. ፀሎት

61. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 18፥39−19፥16 **ወር፡** **ቀን፡**

**ርዕስ፡− ጴንጤናዊው ጲላጦስ በስህተት ፈረደ**

**ዮሐንስ** 18፥ 39. **ነገር ግን እኔ በፋሲካ በዓል አንድ እስረኛ እንድፈታላችሁ ልማድ አላችሁ፤ ስለዚህ 'የአይሁድን ንጉሥ' እንድፈታላችሁ ትፈልጋላችሁን**?"

40. **እነርሱም እንደገና በመጮኽ፣ "የለም፣ እርሱን አይደለም! በርባንን ፍታልን**!" **አሉ። በርባን ግን ወንበዴ ነበረ።**

**ዮሐንስ** 19 ፥1. **ከዚህ በኋላ ጲላጦስ ኢየሱስን ወስዶ አስገረፈው።**

2. **ወታደሮችም የእሾህ አክሊል ጐንጕነው በኢየሱስ ራስ ላይ አደረጉ፤ ሐምራዊ ልብስም አለበሱት፣**

3. **እነርሱ ወደ ኢየሱስ እየመጡ በማፌዝ፣ "የአይሁድ ንጉሥ ሆይ! ሰላም ለአንተ ይሁን**!" **ይሉት ነበር፤ በጥፊም ይመቱት ነበር።**

4. **ጲላጦስ እንደገና ወደ ውጭ ወጥቶ፣ "እነሆ እኔ ምንም በደል እንዳላገኘሁበት እንድታውቁ ኢየሱስን ወደ ውጭ አወጣላችኋለሁ" አላቸው፤**

5. **ስለዚህ ኢየሱስ የእሾህ አክሊል ደፍቶና ሐምራዊ ልብስ ለብሶ ወደ ውጭ ወጣ፤ ጲላጦስም "እነሆ፣ ሰውየው**!" **አላቸው።**

6. **የካህናት አለቆችና ሎሌዎቻቸውም ኢየሱስን ባዩት ጊዜ፣ "ስቀለው! ስቀለው**!" **እያሉ ጮኹ። ጲላጦስም ግን፣ "እኔ ከኢየሱስ ምንም በደል አላገኘሁበትም፤ እናንተ ወስዳችሁ ስቀሉት**!" **አላቸው።**

7. **አይሁድም "እኛ ሕግ አለን፤ ይህ ሰው ራሱን የእግዚብሔር ልጅ ስላደረገ በሕጋችን መሠረት መሞት ይገባዋል" አሉ።**

8. **ይህን ሁሉ ነገር በሰማ ጊዜ ጲላጦስ በይበልጥ ፈራ፤**

9. **ጲላጦስ ወደ ግቢው ተመልሶ ኢየሱስን፣ "አንተ ከየት ነህ**?" **ሲል ጠየቀው። ኢየሱስ ግን ምንም አልመለሰለትም።**

10. **ስለዚህ ጲላጦስ ኢየሱስን፣ "አትነግረኝምን**? **እኔ ልፈታህ ወይም ልሰቅልህ ሥልጣን እንዳለኝ አታውቅምን**?" **አለው፤**

11. **ኢየሱስም፣ "ከእግዚአብሔር ሥልጣን ባይሰጥህ ኖሮ በእኔ ላይ ምንም ሥልጣን ባልኖረ ነበር፤ ስለዚህ እኔን ለአንተ አሳልፎ የሰጠኝ የባሰ ኃጢአት አለበት" አለው።**

12. በሰማ ጊዜ ጲላጦስ ኢየሱስን ሊፈታው ፈለገ፣ አይሁድ ግን፣ "ይህን ሰው ብትፈታው የቄሣር ወዳጅ አይደለህም፣ ራሱን ንጉሥ የሚያደርግ የቄሣር ጠላት ነው" እያሉ ጮኹ።
13. ጲላጦስ ይህን በሰማ ጊዜ ኢየሱስን ወደ ውጭ አውጥቶ "ጠፍጣፋ ድንጋይ" በተባለው ስፍራ በፍርድ ወንበር ተቀመጠ፤ ይህ ስፍራ በዕብራይስጥ ቋንቋ "ገበታ" ይባላል።
14. ቀኑ የፋሲካ በዓል መዘጋጃ፣ ጊዜውም ከቀኑ ስድስት ሰዓት ያህል ነበር። ጲላጦስም አይሁድን፣ "እነሆ ንጉሣችሁ!" አላቸው።
15. እነርሱ ግን፣ "አስወግደው! አስወግደው! ስቀለው!" እያሉ ጮኹ። ጲላጦስም፣ "ንጉሣችሁን ልስቀለውን?" አላቸው። የካህናት አለቆችም፣ "ከቄሣር በቀር ሌላ ንጉሥ የለንም" ብለው መለሱለት።
16. በመጨረሻም ጲላጦስ ኢየሱስን እንዲሰቅሉት አሳልፎ ሰጣቸው። ወታደሮቹም ኢየሱስን ይዘው ወሰዱት፣

ቁ. 1–5 ኢየሱስን በጅራፍ ገርፈው የእሾህ አክሊል አደረጉለት። ሐምራዊውን ልብስ አልብሰው ያፌዙበት ነበር። ኢየሱስ የእኛን ኃጢአት ተሸክሞ በመስቀል ላይ ሞተ።

ቁ. 9–11 ኢየሱስ ሕይወቱን ለመስጠትና እንደ ገና ለመውሰድ ሥልጣን አለው። (ዮሐ፡ 10፥17,18) ኢየሱስ የጶላጦስንና የዓለምን ሥልጣን ወሰን የሚቀበልና የሚወስድ ሰው አይደለም።

ቁ. 9–11 ባሉት ቁጥሮች ጶላጦስ በኢየሱስ ላይ ኃጢአት እንደሌለበት አውቋል። ነገር ግን የሕዝቡን ጩኸት ፈርቶ ኢየሱስን ለሞት አሳልፎ ሰጠ። እኛ ከእግዚአብሔር ይልቅ ሰዎችን ብንፈራ ወደ ጠማማ መንገድ እንደምንሄድ ማስታወስ ይኖርብናል።

**ቁ**. 40 **ምዕ፡** 19፥6 **አይሁድ የእግዚአብሔር ልጅ የሆነውን ኢየሱስን ሰቀሉት። ነገር ግን ሌባውን ባርባንን መረጡ። ይህንን ለማድረግ የራሳቸው ወደሆነው ንጉሥ ወደ ቄሳር ጩኹ። ራሳቸው ግን የእግዚአብሔር ሰዎች መሆናቸውን ካዱ።** (**ቁ**16) **እኛ ዛሬ በማን ጐን ቆመናል**?

**እንጸልይ፡– ጌታ ሆይ፤ ከሰዎች ይልቅ እግዚአብሔርን እንድንፈራ እርዳን፤ አሜን**!

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ**? **ማን ነው**?

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ** (**በስራ ላይ ማዋል**)

7. **ፀሎት**
8. 
9. 
10. _
11. 
12. 

13.

14.68. **የንባብ ክፍል** **ዮሐንስ** 19፡17−27 **ወር፡** **ቀን፡**

**ርዕስ፡− የናዝሬቱ ኢየሱስ የአይሁድ ንጉሥ**

17. **ኢየሱስም መስቀሉን ተሸክሞ፣ "የራስ ቅል" ወደሚባለው ስፍራ ወጣ፤ ይህ ስፍራ በዕብራይስጥ ቋንቋ "ጎልጎታ" ይባላል፤** 18. **በዚያም እነርሱ ኢየሱስን ሰቀሉት፤ ኢየሱስን በመካከል አድርገው፣ ከእርሱ ጋር ሌሎችንም ሁለት ሰዎች በግራና በቀኝ ሰቀሉ።** 19. **ጲላጦስም ጽሑፍ ጽፎ በመስቀሉ ላይ አንጠለጠለው፤ ጽሑፉም፣ 'የናዝሬቱ ኢየሱስ፣ የአይሁድ ንጉሥ' የሚል ነበር።** 20. **ኢየሱስ የተሰቀለበተ ስፍራ ለከተማ ቅርብ ስለ ነበር፣ ከአይሁድ ብዙዎቹ ጽሑፉን አነበቡት፤ ጽሑፉም የተጻፈው በዕብራይስጥ፣ በላቲንና በግሪክ ቋንቋ ነበር።** 21. **የአይሁድ ካህናት አለቆች ጲላጦስን በመቃወም፣ "አንተ 'የአየሁድ ንጉሥ' ብለህ አትጻፍ፤ ነገር ግን፣ 'ይህ ሰው እኔ የአይሁድ ንጉሥ ነኝ' ብሎአል ብለህ ጻፍ" አሉት።** 22. **ጲላጦስም፣ "እኔ የጻፍሁትን ጽፌአለሁ" ብሎ መለሰ።**

23. **ወታደሮቹ ኢየሱስን ከሰቀሉት በኋላ፣ ልብሶቹን ወስደው፣ ለእያንዳንዱ ወታደር አንድ ክፍል እንዲደርስ በአራት ከፋፈሉአቸው፤ እጀ ጠባቡም ከላይ እስከ ታች አንድ ወጥ ሆኖ ያለ ስፌት የተሠራ ነበር።**

24. **ስለዚህ ወታደሮቹ፣ "ዕጣ ተጣጥለን ለሚደርሰው ይድረስ እንጂ አንቅደደው" ተባባሉ። ይህም የሆነው፣ "ልብሴን ተከፋፈሉት፣ በእጀ ጠባቤም ላይ ዕጣ ተጣጣሉ" የሚለው የመጽሐፍ ቃል እንዲፈጸም ነው። ወታደሮቹ የደረጉትም ይህንኑ ነው።** 25. **በኢየሱስ መስቀል አጠገብ እናቱን የእናቱ እኅት፣ የቀልዮጳ ሚስት ማርያምና መግደላዊት ማርያመ ቆመው ነበር፤** 26. **በዚያም ኢየሱስ እናቱን የሚወደውን ደቀ መዝሙር አጠገቡ ቆመው ባያቸው ጊዜ፤ እናቱን፣ "እናቴ ሆይ! እነሆ፣ ልጅሽ ይኸው" አላት፣** 27. **ከዚህ በኋላ ኢየሱስ ደቀ መዝሙሩን፣ "እናትህ ይህችው" አለው። ከዚያን ጊዜ ጀምሮ ይህ ደቀ መዝሙር ወደ ቤቱ ወሰዳት።**

**ቁ**. 17,18 **ኢየሱስ የራሱን ሞት እንደ ክብር ቆጠረ። ስለዚህ ብቻውን በዚህ መንገድ ሄደ። ዛሬ እኛ ስለ ኢየሱስ ብለን በዚህ መንገድ ልንሄድ እንችላለን?**

**ቁ**. 19−22 **ኢየሰስ በመስቀል ላይ የተሰቀለው ሥቅለት ሳይሆን የእግዚአብሔር ልጅና የእስራኤል ንጉሥ መሆኑን የሚገልጽ የክብር ሁኔታ ነው። የኢየሱስ በመስቀል**

ላይ የመሰቀል ሁኔታ ከሁሉ ወገንና ቋንቋ የሚኖሩ ሰዎችን ወደ እግዚአብሔር ለማምጣት ነው። (ምዕ. 12፥32) ጶላጦስ በሦስት ቋንቋ "የናዝሬቱ ኢየሱስ የአይሁድ ንጉሥ" ብሎ ጻፈ። ይህ ሦሰት ቋንቋ ሙሉ ወገኖችን የሚያጠቃልል ስለሆነ ሰዎች ሁሉ ወደ ኢየሱስ እንዲመጡ ማድረጉ አያስገርምም?

**ቁ**. 25-27 ኢየሱስ ለደቀ መዛሙርቱ ዮሐንስ እናትህን ተመልከት አለ። ይህ ቃል የኢየሱስ እናት ዮሐንስ እናት እንደሆነች ይገልጻል። እንዲሁም የእግዚአብሔር መንግሥት ቤተሰቦች ይሆናል ማለት ነው። የእኛም ቤተሰቦች የእግዚአብሔር መንግሥት ቤተሰቦች ይሆናሉ።

እንጸልይ፡- ጌታ ሆይ፤ እኛ ክርስቲያኖች ኢየሱስ በሄደበት ክበር መንገድ በደስታ እንድንሄድ እርዳን፤ አሜን!

1. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ

2. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት

3. እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?

4. የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና

5. ትምህርት

6. ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)

7. ፀሎት

69. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 19፥28−30 **ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፡− በመስቀል ላይ ኢየሱስ የተናገረው ሰባት ምሳሌዎች**

28. **ከዚህ በኋላ ኢየሱስ ሁሉ ነገር እንደ ተፈጸመ አውቆ፣ በቅዱስ መጽሐፍ የተጻፈው ቃል እንዲፈጸም፣ "ተጠማሁ" አለ።**

29. **እዚያ ሆምጣጤ ወይን የሞላበት ዕቃ ተቀምጦ ነበር፤ ስለዚህ እዚያ ነበሩ ሰዎች፣ ሆምጣጤውን በሰፍነግ ሞሉና በሂሶጵ እንጨት አንጠልጥለው ወደ አፉ አቀረቡለት፤**

30. **ኢየሱስም ሆምጣጤውን ከቀመሰ በኋላ "ተፈጸመ!" አለ። ራሱን ዘንበል አድርጎም ነፍሱን ሰጠ።**

**ዮሐንስ** 19፥28−30 **ኢየሱስ ቃሉን ለመፈጸም "ተጠማሁ" አለ። ይህ ማለት "ሁሉንም ጨርሶ የመታዘዝን ሕይወት ያሳያል" ማለት ነው።**

**ማቴ**. 27፥45−46 **"ኤሎሄ ኤሎሄ ላማ ሰባቅ ታኒ" አለ። ይህ ማለት ትርጉሙ ደግሞ አምላኬ አምላኬ ለምን ተውከኝ ማለት ነው።**

**ማርቆ**. 15፥33−34 **"ኤሎሄ ኤሎሄ ላማ ሰባቅ ታኒ" አለ። ይህ ማለት ትርጉሙ ደግሞ አምላኬ አምላኬ ለምን ተውከኝ ማለት ነው።**

**ሉቃ**. 23፥34 **"አባቴ ሆይ የሚያደርጉትን ስለማያውቁ ይቅር በላቸው" አለ።**
**ሉቃ**. 23፥43 **"በእውነት እልኋለሁ ዛሬውኑ ከእኔ ጋር በገነት ትሆናለህ" አለ።**
**ሉቃ**. 23፥46 **"አባቴ ሆይ እነሆ ነፍሴን በእጅህ አደራ እሰጣለሁ" አለ።**

**ዮሐንስ** 19፥28−30 **ኢየሱስ ቃሉን ለመፈጸም ተጠምቶ ነበረ። ይህ ማለት ኢየሱስ ሁሉንም ሥራ ለመፈጸም የሚሠራና የሚታዘዝ ማለት ነው። የእኔን ሥራ ጨረስሁ ወይም ፈጸምኩ ማለት ሁሉንም የመታዘዝ ሕይወት ያሳያል።**
**ሉቃስ** 23፥34 **ኢየሱስ በመስቀል ላይ ራሱን በሚስማር ሲቸነክሩ እግዚአብሔር ለእነርሱ ይቅር እንዲላቸው ጸለየ። በዚህ ጸሎት እኛም ይቅርታን ተቀበልን። ስለዚህ**

**በዚህ ቀን የሚሄዱት በፊት ጠላቶችና ቅናትን የሚያደርጉ ነበሩና ከይቅርታ በኋላ ተወው።**

**ሉቃ.** 23፥46 **ኢየሱስ እግዚአብሔር የእርሱ አባት መሆኑን አልተጠራጠረም። የራሱንም መንፈስ ለእግዚአብሔር ከሰጠ በኋላ ሞተ።**

**አንጸልይ፡- ጌታ ሆይ፤ ኢየሱስ የሰዎችን ኃጢአት ይቅር እንዳለው እኛም ደግሞ የሌሎችን ኃጢአት ይቅር እንድንል እርዳን፤ አሜን!**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

70. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 19፥31−42 **ወር፡ ቀን፡**

## **ርዕስ፡− የንጉሥ ሞትና ሥርዓተ ቀብር**

31. **ዕለቱ ለሰንበት መዘጋጃ ቀን ነበር፣ አይሁድ፣ የተሰቀሉትን ሰዎች ጭን ሰብረው፣ አስከሬናቸውን ከመስቀል እንዲያወርዱአቸው ጲላጦስን ለመኑት፤ ይህንንም ያደረጉበት ምክንያት የሰንበት ዝግጅት ቀን ስለ ነበረና ያ ሰንበትም ትልቅ በዓል ስለ ሆነ፣ በሰንበት ቀን ሥጋቸው በመስቀል ላይ እንዳይሆን ነበር።**

32. **ስለዚህም ወታደሮቹ መጥተው ከክርስቶስ ጋር ተሰቅሎ የነበረውን የመጀመሪያውን ሰው ጭን ሰበሩ፣ ደግሞም የሌላውን ጭን ሰበሩ።**

33. **ወደ ኢየሱስ በመጡ ጊዜ ግን፣ እርሱ ቀደም ሞቶ ስላገኙት ጭኑን አልሰበሩም።**

34. **ነገር ግን ከወታደሮቹ አንዱ፣ የኢየሱስን ጐን በጦር ወጋው፤ ወዲያውኑ ከጐኑ ደምና ውና ወጣ።**

35. **ይህን ያየው ሰው ምስክርነቱን ሰጥቶአል፣ ምስክርነቱም እውነት ነው፣ እውነትን እንደሚናገርም ያውቃል፣ እናንተም እንድታምኑ ይመሰክራል።**

36. **ይህም የሆነው፣ "ከእርሱ አንድ አጥንት እንኳ አይሰበርም" የሚለው የቅዱስ መጽሐፍ ቃል እንዲፈጸም ነው።**

37. **ደግሞም በሌላው የቅዱስ መጽሐፍ ክፍል "እነርሱ የወጉትን ያዩታል" ይላል።**

38. **ከዚህ በኋላ የአርማትያሱ ዮሴፍ የኢየሱስን በድን ለመውሰድ ጲላጦስን ለመነው፣ ዮሴፍም አይሁድን ስለ ፈራ በስውር የኢየሱስ ደቀ መዝሙር ነበር። እርሱም ጲላጦስን ካስፈቀደ በኋላ መጥቶ በድኑን ወሰደ።**

39. **ከዚህ ቀደም በሌሊት ወደ ኢየሱስ መጥቶ የነበረው ኒቆዲሞስ አንድ መቶ ሊትራ ያህል የሚመዝን የከርቤና የእሬት ቅልቅል ይዞ መጣ።**

40. **ሁለቱ ሰዎች የኢየሱስን በድን ወስደው እንደ አይሁድ አገናነዝ ልማድ ከሽቶ ጋር በቀጭን ልብስ ከፈኑት።**

41. **ኢየሱስ ተሰቅሎ በነበረበት ቦታ አንድ የአትክልት ስፍራ ነበረ፤ በዚያም የአትክልት ስፍራ ውስጥ ማንም ያልተቀበረበት አዲስ መቃብር ነበር።**

42. **ዕለቱ ለአይሁድ የሰንበት ዝግጅት ቀን ስለ ነበረና መቃብሩም ቅርብ ስለ ነበረ የኢየሱስን በድን በዚያ ቀበሩት።**

**ቁ**. 31−33,36 ኢየሱስ የዓለምን ኃጢአት ተሸክሞ እንደ ፋሲካ ጠቦት ሞተ። የኢየሱስ አጥንት አልተሰበረም። ይህ የሚያሳየው የፋሲካ ጠቦትን ነው። (ዘጸ. 22፥46 ዘዳ.9፥12) ኢየሱስ ራሱ በመስቀል ላይ በመሞት የእኛን ሁሉ ኃጢአት አነጻ።

**ቁ**. 34−35 ከኢየሱስ ጐን ደምና ውሃ ፈሰሰ። በመንፈስ ቅዱስ የሚሰጠው የውሃውን ጊዜ ያስታውቃል። ደም ማለት ለእኛ የዘላለም ሕይወትን የሚሰጠው የኢየሱስ ደምን ማመልከቱ ነው። (ዮሐ. 6፥53) ውሃ ማለት እኛ ለዘላለም እንዳንጠማ የሚያደርግ የሕይወት ውሃ ማለት ነው። (ዮሐ. 4፥14) ከእኛ ሆድ እንደሚፈስ የሕይወት ወንዝ ማለት መንፈስ ቅዱስን የሚያመለክት ነው። (ዮሐ. 7፥38) ኢየሱስ በመስቀል ላይ ሞቶ ለእኛ ሕይወትንና የመንፈስ ቅዱስ ስጦታ የሰጠው ከእግዚአብሔር ጋር ቅን ግንኙነት እንድናደርግና በየቀኑ በዘላለም ሕይወት እንድንኖር ነው።

**ቁ**. 41,42 ኢየሱስን በአዲስ መቃብር ውስጥ ቀበሩ። የሕይወት ጌታ እንደ ሚሞቱ አስቀድሞ ድልን የሚያሳይ መቃብር ነው። አሮጌ የሰዎችን ኃጢአት ዛሬ ኢየሱስ በአዲስ መቃብር ውስጥ ይቀብራል። ስለዚህ ከኢየሱስ ትንሣኤ ጋር በአዲስ ሕይወት እንደገና እንኖራለን። (ሮሜ 6፥5)

**ቁ**. 38−40 ለአርማቲዮስ ዮሴፍ ጰላጦስን በብርቱ አስክሬኑን ወስዶ በራሱ መቃብር ለምኖ ቀበረ። ከዚያ በኋላ በሌሊት ወደ ኢየሱስን ብዙ ከርቤንና እሬትን በማምጣት በስርዓት ቀብር ላይ አፍስሰው ነበር።

**እንጸልይ፦**− ጌታ ሆይ፣ ኃጢአቶቻችን በጌታ ተቀብሮ በአዲስ ሕይወት እንድንወለድ እርዳን፤ አሜን።

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

71. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 20፥1−10 **ወር፡ ቀን፡**

**ርዕስ፡− ባዶ መቃብር**

1. **እሑድ ጠዋት በማለዳ፣ በማለዳ ገና ጨለማ ሳለ፣ መግደላዊት ማርያም ወደ ኢየሱስ መቃብር ሄደች፤ እዚያም እንደደረሰች መቃብሩ ተዘግቶበት የነበረው ድንጋይ ከመቃብሩ በር ተንከባሎ አየች።**

2. **ስለዚህ ማርያ ወደ ስምዖን ጴጥሮስና ኢየሱስ ወደሚወደው ወደ ሌላው ደቀ መዝሙር እየሮጠች ሄደችና፣ "ጌታን ከመቃብሩ አውጥተው ወስደውታል፤ የት እንዳኖሩት አናውቅም" አለቻቸው።**

3. **ከዚያም ጴጥሮስና ሌላው ደቀ መዝሙር መጥተው ወደ መቃብሩ ሄዱ።**

4. **ሁለቱም አብረው ይሮጡ ነበር፤ ሌላው ደቀ መዝሙር ከጴጥሮስ ይበልጥ ፈጥኖ ሮጠና ቀድሞ ወደ መቃብሩ ደረሰ።**

5. **ጐንበስ ብሎም ወደ መቃብሩ ቢመለከት የከፈኑ ጨርቅ በዚያው እንዳለ አየ፣ ነገር ግን ወደ መቃብሩ ውስጥ አልገባም።** 6. **ስምዖን ጴጥሮስም ተከትሎት መጣና ወደ መቃብሩ ውስጥ ገባ፤ ጴጥሮስም የከፈኑን ጨርቅ እዚያ ተቀምጦ አየ፤** 7. **ጴጥሮስም በኢየሱስ ራስ ላይ ተጠምጥሞ የነበረውን ጨርቅ አየ፣ ይህም ጨርቅ ከከፈኑ ተለይቶ እንደ ተጠቀለለ ነበር።**

8. **ከዚያም አስቀድሞ ከመቃብሩ የደረሰው ሌላው ደቀ መዝሙር ወደ ውስጥ ገባ፣ አይቶም አመነ፣**

9. **ኢየሱስ ከሙታን መነሣት እንዳለበት ገና የቅዱስ መጽሐፍ ቃል ስላልተረዱ ነበር።**

10. **ከዚያም በኋላ ሁለቱም ደቀ መዛሙርት ተመልሰው ወደ ቤታቸው ሄዱ።**

**ቁ**. 1,2 **መግደላዊት ማርያም ክፍት መቃብር አይታ የኢየሱስን መነሣት አላሰበችም። በራስዋ እምነትና አመለካከት ኢየሱስ መስቀል ላይ እስከሚሰቀል ድረስ ስትከተል ነበር። ነገር ግን አሁን ትንሣኤውን በእምነት አልደረሰችም እኛ ደግሞ እንደ ማርያም የኢየሱስን ትንሣኤ በጥርጣሬ ተመለከትን**?

**ቁ**. 3−10 **የማርያምን ቃል ሰምተው ጴጥሮስና ዮሐንስ ወደ መቃብር ሮጡ። ዮሐንስም ባዶ መቃብሩን የትንሣኤ ማስረጃ አይቶ አመነ። የተነሣውን ኢየሱስን ከመገናኘቱ በፊት የከፈኑን ጨርቅ ብቻ አይቶ ያመነ ሰው ነው። ቶማስ "ጣቴን በሚስማር በተወጋው እጆቹ ውስጥና እጄንም በጐኑ ቁስል አስገብቸ አምናለሁ" ብሎ ተናገረ።**

(ዮሐ፡ 20፥24,25) ነገር ግን የዮሐንስ እምነት ከቶማስ እምነት ይለያል። እኛ ደግሞ እንደ ዮሐንስ ቃሉን ሰምተን እንድናምን ያስፈልጋል።

**ቁ**. 9 ደቀ መዛሙርቱ ኢየሱስ በመጽሐፍ ቅዱስ የተናገረውን ከሞት እንደ ገና እንደሚነሣ ከቃሉ አላስተዋሉም። እኛ ቃሉን ስንሰማ ገና ትንሣኤውን አላመንንም? ከኢየሱስ ጋር እኛ ደግሞ በክብር ሥጋ ትንሣኤውን አምነንና ለሌሎች የትንሣኤ ወንጌል እንሰብካለን።

**እንጸልይ፡-** ጌታ ሆይ፤ የትንሣኤ ኢየሱስን አምነን ለሌሎች ሰዎች የትንሣኤውን ወንጌል እንድንሰብክ እርዳን፤ አሜን!

1. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ

2. ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት

3. እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?

4. የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና

5. ትምህርት

6. ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)

7. ፀሎት

72. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 20፥11−23 **ወር፡** **ቀን፡**

**ርዕስ፦ የትንሣኤው ስጦታ**

11. ማርያም ግን ከመቃብሩ ውጭ ቆማ ታለቅስ ነበር፤ እያለቀሰችም ጐንበስ ብላ ወደ መቃብሩ ውስጥ ተመለከተች።

12. ማርያም የኢየሱስ ሥጋ በነበረበት ቦታ፣ ነጫጭ ልብስ የለበሱ ሁለት መላእክት አንዱ በራስጌ ሌላው በግርጌ ተቀምጠው አየች።

13. መላእክትም ማርያምን፣ "አንቺ ሴት! ለምን ታለቅሻለሽ?" አሉአት። ማርያም፣ "ጌታዬን ወስደውታል፤ የት እንዳኖሩትም አላውቅም" አለች።

14. ማርያም ይህን ብላ ዘወር ስትል ኢየሱስ በዚያው ቆሞ አየችው፤ ኢየሱስ መሆኑን ግን አላወቀችም።

15. ኢየሱስ ማርያን፣ "አንቺ ሴት፣ ለምን ታለቅሻለሽ? ማንንስ ትፈልጊአለሽ?" አላት። ማርያም የአትክልቱ ቦታ ጠባቂ መስሎአት፣ "ጌታ ሆይ! አንተ ወስደኸው እንደ ሆነ የት እንዳኖርከው እባክህ ንገረኝ፤ እኔ እወስደዋለሁ" አለችው።

16. ኢየሱስም፣ "ማርያም" አላት። ማርያም ወደ እርሱ ዘወር ብላ በአራማይክ ቋንቋ፣ "ረቡኒ! አለችው፣ ትርጕሙም "መምህር ሆይ" ማለት ነው።

17. ኢየሱስ ማርያን፣ "እኔ ገና ወደ አባቴ አላረግሁምና አትንኪኝ ነገር ግን ወደ ወንድሞቼ ሂጂና፣ 'እኔ ወደ አባቴና ወደ አባታችሁ፣ ወደ አምላኬና ወደ አምላካችሁ ዐርጋለሁ' ብሎአል ብለሽ ንገሪያቸው!" አላት።

18. ስለዚህ መግደላዊት ማርያም ወደ ደቀ መዛሙርቱ ሄዳ "ጌታን እኮ አየሁት!" አለች፣ ኢየሱስ ያላትንም ነገረቻቸው።

19. በዚያው በሳምንቱ በመጀመሪያው ቀን እሑድ ማታ ደቀ መዛሙርቱ አይሁድን በመፍራት በሮቹን ቈልፈው ተሰብስበው ሳሉ፤ ኢየሱስ ደቀ መዛመርቱ ወደ ተሰበሰቡበት ቤት ገባ፤ በመካከላቸውም ቆሞ፣ "ሰላም ለእናንተ ይሁን" አላቸው።

20. ይህንንም ብሎ እጆቹንና ጐኑን አሳያቸው፤ ደቀ መዛሙርቱም ጌታን ባዩ ጊዜ ደስ አላቸው።

21. ኢየሱስም እንደገና፣ "ሰላም ለእናንተ ይሁን፣ አብ እኔን እንደ ላከኝ፣ እኔም እናንተን እልካችኋለሁ" አላቸው።

22. ይህን ካለ በኋላም፣ እፍ አለባቸውና እንዲህ አላቸው፣ "መንፈስ ቅዱስን ተቀበሉ፣ 23. እናንተ የሰዎችን ኃጢአት ይቅር ብትሉ ይቅር ይባልላቸዋል፤ እናንተ የሰዎተን ኃጢአተ ይቅር ባትሉ ግን፣ ይቅር አይባልላቸውም"

**ቁ**. 17 የኢየሱስ ትንሣኤ ለእኛ ከኢየሱስ ጋር አንድ ቤተሰብ እንድንሆን የበረከትን ጊዜ ከፈተልን። ኢየሱስ ለደቀ መዛሙርቱ "ወንድሞች" እንዲሁም እግዚአብሔርን "አባት" ብለው እንዲጠሩ የቤተሰብነት ልዩ መብት ሰጠ።

**ቁ**. 19-21 የትንሣኤው ኢየሱስ የሠላምና የደስታ ጊዜ ከፍቶ ሰጠ። ኢየሱስ ለደቀ መዛሙርቱ "የትንሣኤ ጌታ መጥቷል" ብሎ ሠላምን ሰብኮ ማንም የማይወስደውን ደስታን ገለጸላቸው። (ዮሐ 16፥20-22) አሁን ለምን ዓይነት ችግሮች ወይንም ምን የሚያሳስቡ ነገሮች ላይ ፈርተናል? የትንሣኤው ኢየሱስ የሚሰጠውን የሠላምን ስጦታ ተቀበሉ!

**ቁ**. 21 በትንሣኤው ስጦታ ሠላምና ደስታን አለማምዶ ኢየሱስ ደቀ መዛሙርቱን ወደ ዓለም ላካቸው። ኢየሱስ ደቀ መዛሙርቱን ወደ ዓለም ልኮ የሠላምን ሥራ እንዲፈጽሙ አደረጋቸው። እኛ ደግሞ ጌታ የላከን የሠላም ሰዎች ነን። ይህ ድንቅ ሠላምን ለማን አሳይተን ሰጠን?

**ቁ**. 11-14 በኢየሱስ ትንሣኤ ማርያም አጥብቃ አዝና ነበር። ምክንያቱም ማርያም ትንሣኤውን ስላላመነች ነበር። እኛ ደግሞ ስለ ትንሣኤው ቃል በፍጹም አምነናልን?

**እንጸልይ**፦ ጌታ ሆይ፤ ለምናገኛቸው ሰዎች የትንሣኤው ኢየሱስ ሠላምን እንድንሰብክ እርዳን፤ አሜን!

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ**? **ማን ነው**?

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ** (**በስራ ላይ ማዋል**)

7. **ፀሎት**

73. **የንባብ ክፍል  ዮሐንስ** 20፥24−31 **ወር፡**  **ቀን፡**

**ርዕስ፦ የእኔ ጌታና የእኔ አምላክ**

24. **ከአሥራ ሁለቱ አንዱ የሆነው፣ ዲዲሞስ የተባለው ቶማስ፣ ኢየሱስ በመጣ ጊዜ ከደቀ መዛሙርቱ ጋር አልነበረም።**

25. **ስለዚህ ሌሎች ደቀ መዛሙርት ቶማስን፣ "ጌታን አየነው" አሉት። ቶማስ ግን፣ "በምስማር የተወጉትን እጆቹን ካላየሁና ጣቴን በምስማር በተወጋው ውስጥ ካላገባሁ፣ እጄንም በጐኑ ቍስል ካላገባሁ አላምንም" አላቸው።**

26. **ከስምንት ቀን በኋላም፣ ደቀ መዛሙርቱ በቤት ውስጥ ነበሩ፣ ቶማስም ከእነርሱ ጋር ነበር፣ በሮቹ ተቈልፈው ነበር፣ ኢየሱስ ግን መጥቶ በመካከላቸው ቆመና፣ "ሰላም ለእናንተ ይሁን" አላቸው።**

27. **ከዚህ በኋላ ኢየሱስ ቶማስን፣ "ጣትህን ወደዚህ አምጣና እጆቼን እይ፤ እጅህንም አምጣና በጐኔ ውስጠ አግባው፤ አትጠራጠር፣ እመን" አለው።** 28. **ቶማስም ኢየሱስን፣ "ጌታዬ! አምላኬም!" ሲል መለሰለት።**

29. **ኢየሱስም ቶማስን፣ "አንተሰ ስለ አየኸኝ አምነሃል፣ ሳያዩኝ የማያምኑ ግን ብፁዓን ናቸው" አለው።**

30. **ኢየሱስ በዚህ መጽሐፍ ያልተጻፉ ሌሎች አያሌ ታምራዊ ምልክቶችን በደቀ መዛሙርቱ ፊት አድርጓል፣**

31. **ነገር ግን ኢየሱስ እርሱ ክርስቶስ፣ የእግዚአብሔር ልጅ መሆኑን እንድታምኑና፣ አምናችሁም በኢየሱስ ስም የዘለዓለም ሕይወትን እንድታገኙ ይህ ተጽፎአል።**

**ቁ**. 26,27  **ኢየሱስ ለደቀ መዛሙርቱ በሚገለጥበት ጊዜ በዚያ ስፍራ ቶማስ አልነበረም። አሁን ለቶማስ እምነትን ለመስጠት እንደገና መጣ። ለደቀ መዛሙርቱ የሰጠው የሠላም ቃል እንደገና ከቶማስ ጋር ደቀ መዛሙርቱ ተሰብስበው እያሉ ተናገረ።**

**ቁ**. 28  **ቶማስም ኢየሱስን  "የእኔ ጌታዬና አምላኬ" ብሎ ንሰሓ ገባ። ይህ ቃል ማለት ኢየሱስ ከእግዚአብሔር ጋር እኩል ክብርን ይቀበላል ማለት ነው።** (**ዮሐ፡** 5፥23) **ደግሞም በእኛ ሕይወት ኢየሱስ ጌታ ስለሆነ እኛ ደግሞ ኢየሱስ ጌታ እንደሆነ የንሰሓን ቃል ተናገርን**?

**ቁ.** 30,31 **በዮሐንስ በኩል ይህ ወንጌል የተጻፈው የኢየሱስ ትንሣኤን ያላዩ ሰዎች አምነው የዘላለምን ሕይወት እንዲያገኙ ምቹ ጊዜን ለመስጠት ነው።**

**ቁ.** 29 **ኢየሱስን አይተው ካመኑት ይልቅ ያላዩ ሰዎች ቃሉን ሰምተው ያመኑት እነርሱ ይበልጥ የተባረኩ ናቸው።**

**እንጸልይ፡– ጌታ ሆይ፤ እኛ ሙሉ ቃልህን ሰምተን እንድናምን ዘንድ እርዳን፤ አሜን**!

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ**? **ማን ነው**?

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ** (**በስራ ላይ ማዋል**)

7. **ፀሎት**

74. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 21፥1−14 **ወር፡ ቀን፡**

## ርዕስ፡− ኢየሱስ ሦስት ጊዜ ተገለጠ

1. **ከዚህ በኋላ ኢየሱስ በጥብርያዶስ ባሕር አጠገብ፣ እንደገና ለደቀ መዛሙርቱ እንደገና ተገለጠ፤ የተገለጠውም እንደሚከተለው ነው፤**

2. **ስምዖን ጴጥሮስ፣ ዲዲሞስ የተባለው ቶማስ፣ የቃና ዘገሊላው ናትናኤል፣ የዘብዴዎስ ልጆችና ከደቀ መዛሙርቱ ሌሎች ሁለት አብረው ነበሩ።**

3. **ስምዖን ጴጥሮስ "ዓሣ ለማጥመድ መሄዴ ነው" አላቸው። እነርሱም፣ "እኛም ከአንተ ጋር እንሄዳለን" አሉት፤ ወጥተውም ሄዱና ወደ ጀልባ ገቡ፤ ነገር ግን በዚያች ሌሊት አንድ ዓሣ እንኳ አልያዙም።**

4. **ሲነጋም፣ ኢየሱስ በባሕሩ ዳርቻ ቆመ፤ ደቀ መዛሙርቱ ግን ኢየሱስ መሆኑን አላወቁም ነበር።**

5. **ኢየሱስም ደቀ መዛሙርቱን፣ "ልጆች ሆይ! አንዳች ዓሣ አላችሁን?" አላቸው። እነርሱም፣ "ምንም የለንም" አሉት።**

6. **ኢየሱስም ደቀ መዛሙርቱን፣ "መረባችሁን ከጀልባው በስተቀኝ ጣሉ፣ ዓሣ ታገኛላችሁ" አላቸው። ስለዚህ ደቀ መዛሙርቱ መረቡን በባሕሩ ውስጥ ጣሉት፤ ብዙ ዓሣም ከመያዛቸው የተነሣ መረቡን መጐተት አቃታቸው።**

7. **በዚህ ጊዜ ኢየሱስ የሚወድደው ደቀ መዝሙር ጴጥሮስን፣ "ጌታ ነው እኮ!" አለው። ስምዖን ጴጥሮስ "ጌታ ነው" ማለትን በሰማ ጊዜ ለሥራ ብሎ ልብሱን አውልቆ ስለ ነበረ ወዲያው ልብሱን ለበሰና ወደ ባሕሩ ዘሎ ገባ።**

8. **ሌሎች ደቀ መዛሙርት ግን ከባሕሩ ዳርቻ የራቁት መቶ ሜትር ያህል ብቻ ስለ ነበር፣ ዓሣ የሞላበትን መረብ እየሳቡ በጀልባ መጡ።**

9. **ደቀ መዛሙርት ወደ ምድርም በደረሱ ጊዜ፣ ዓሣ በላዩ የነበረበት የከሰል ፍምና እንጀራ አዩ።**

10. **ኢየሱስም ደቀ መዛሙርቱን፣ "አሁን ካጠመዳችሁት ዓሣ አምጡ" አላቸው።**

11. **ስለዚህ ስምዖን ጴጥሮስ ወደ ጀልባው ገብቶ መረቡን ወደ ምድር ጐተተው፣ መረቡንም መቶ አምሳ ሦስት ትልልቅ ዓሣ ሞልተውት ነበር፣ ይህን ያህል ብዙ ዓሣ ቢይዝም መረቡ አልተቀደደም።**

12. ኢየሱስም ደቀ መዛሙርቱን፣ "ኑ፣ ቊርስ ብሉ" አላቸው። ጌታ ኢየሱስ መሆኑን ሁሉም አውቀው ስለ ነበር፣ ከደቀ መዛሙርቱ አንድ እንኳ፣ "አንተ ማን ነህ?" ብሎ ሊጠይቀው የደፈረ አልነበረም።
13. ከዚያም ኢየሱስ መጥቶ እንጀራውንና ዓሣውን አንሥቶ ሰጣቸው።
14. እንግዲህ ኢየሱስ ከሙታን ከተነሣ በኋላ ለደቀ መዛሙርቱ ሲታይ ይህ ሶስተኛ ጊዜ ነው።

**ቁ**. 1,6 አዳም ኃጢአትን ሠርቶ ሲሠወር እግዚአብሔር ወደ አዳም ሄዶ አገኘው። እንደዚሁም ኢየሱስ በዓለም እየተመላለሰ የወደቁትን ደቀ መዛሙርቱን አገኘ። እኛ ጌታን ብንተው ጌታ ግን ከቶ እኛን አይተወንም።

**ቁ**. 5,6,11 ኢየሱስ ደቀ መዛሙርቱ ብዙ ዓሣ ለመያዝ መጥተው የመጀመርያ ሥራ በሚሰሩበት ጊዜ እንደ ገና ተገልጦ ብዙ ነፍሳትን ወደ ጌታ እንዲያመጡ ተናገራቸው። (ሉቃ፥ 5፥4—11) ዛሬ በዚህ ቀን እኛ የጠፉትን ነፍሳት ለማዳን የኢየሱስን ጥሪ ሰምተን ተልዕኮአችንን እንድንፈጽም ያስፈልጋል።

**ቁ**.9—13 ኢየሱስ የደቀ መዛሙርቱን ውድቀት ለመፈወስ ፈልጎ የፍቅር ግንኙነት ለማካፈል በዓል አዘጋጅቶ ጠራቸው። ጴጥሮስ እሳት ሲሞቅ ኢየሱስን የካደውን እሳቱን እንዳስታውስ አደረገ። (ዮሐ፥ 18፥18)

**ቁ**. 2—4 ተልዕኮአቸውን ረስተው ወደ ዓሣ መያዝ ሥራ መመለስ ደቀ መዛሙርት ፊት ረዥም ለሊትና ባዶ ጀልባ ጌታን አለማስተዋልና መንፈሳዊ ጨለማነት ነው። አሁን እኛ በመንፈሳዊ ጨለማ መንገድ እየሄድን ፍሬን ለማፍራት እንሞክራለን። እግዚአብሔር የሰጠውን ተልዕኮ እንዳንረሳ ሁል ጊዜ ራሳችንን ልንመረምር ያስፈልገናል።

**እንጸልይ፡- ጌታ ሆይ፤ የእኛ ኃጢአታችንን ሁሉ ይቅር እንድትልና እኛም የፍቅር ግንኙነት እንድንከፋፈል እርዳን፤ አሜን!**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**

75. **የንባብ ክፍል ዮሐንስ** 21፥15-25 **ወር፡ ቀን፡**

## ርዕስ፡- እንደ ገና የወንጌል ሥራ

15. እነርሱ ቊርስ ከበሉ በኋላ ኢየሱስ ስምዖን ጴጥሮስን፣ "የዮና ልጅ ስምዖን ሆይ! እነዚህ ከሚወዱኝ ይበልጥ ትወደኛለህን?" አለው። ጴጥሮስም "አዎ፣ ጌታዬ ሆይ! እኔ እንደምወድህ አንተ ታውቃለህ" ሲል መለሰለት። ኢየሱስም፣ "ጠቦቶቼን መግብ" አለው።

16. ኢየሱስም ለሁለተኛ ጊዜ፣ "የዮና ልጅ ስምዖን ሆይ፥ እኔን ትወደኛለህን?" አለው። ጴጥሮስም "አዎን፣ ጌታ ሆይ፣ እንደምወድህ አንተ ታውቃለህ" አለው። ኢየሱስም፣ "በጎቼን ጠብቅ" አለው።

17. ኢየሱስም ሶስተኛም ጊዜ፣ "የዮና ልጅ፣ ስምዖን ሆይ፣ እኔን ትወደኛለህን?" አለው። ጴጥሮስም ሶስተኛ ጊዜ ኢየሱስ፣ 'ትወደኛለህን?' ብሎ ስለ ጠየቀው አዘነና፣ "ጌታ ሆይ፥ አንተ ሁሉን ታውቃለህ፤ እንደምወድህም ታውቃለህ" አለው። ኢየሱስም እንዲህ አለው፣ "በጎቼን መግብ።

18. በእውነት እልገለሁ፣ ወጣት ሳለህ ልብስህን ራስህ ለብሰህ ወደ ፈለግህበት ትሄድ ነበር፣ በሸመገልክ ጊዜ ግን አንተ እጆችህን ትዘረጋና ሌላ ሰው ያስታጥቅሃል፤ ወደማትፈልግበትም ይወስድሃል።"

19. ኢየሱስ ይህን ያለው ጴጥሮስ በምን ዓይነት ሞት እግዚብሔርን እንደሚያከብረው ለማመልከት ነው። ከዚህ በኋላም ኢየሱስ ጴጥሮስን፣ "ተከተለኝ" አለው።

20. ጴጥሮስ ወደ ኋላው ዘወር ሲል፣ ኢየሱስ የሚወድደው ደቀ መዝሙር ሲከተለው አየ፤ ይህ ደቀ መዝሙር በእራት ጊዜ ወደ ኢየሱስ ተጠግቶ፣ "ጌታ ሆይ፣ አሳልፎ የሚሰጥህ ማን ነው?" ብሎ የጠየቀው ነው።

21. ጴጥሮስ እርሱን አየና "ጌታ ሆይ! ይህስ ሰው ምን ይሆናል?" ሲል ኢየሱስን ጠየቀ።

22. ኢየሱስም፣ "እኔ እስክመለሰ ድረስ በሕይወት እንዲኖር ብፈልግ እንኳ አንተን ምን ቸገረህ? አንተ ተከተለኝ" አለው።

23. በዚህ ምክንያት ይህ ደቀ መዝሙር አይሞትም የሚል ወሬ በወንድሞች መካከል ተሰራጨ። ነገር ግን ኢየሱስ፣ "እኔ እስክመለሰ ድረስ በሕይወት እንዲኖር ብፈልግ አንተን ምን ቸገረህ?" አለው እንጂ እንደማይሞት አልነገረውም።

24. ሰለ እነዚህ የሚመሰክረውና ይህን የጻፈው ይህ ደቀ መዝሙር ነው፣ እኛ የእርሱም ምስክርነት እውነት እንደ ሆነ እናውቃለን።
25. ኢየሱስ ያደረጋቸው ሌሎች ብዙ ነገሮች ደግሞ አሉ። እኔ እንደሚመስለኝ እርሱ የደረጋቸው ነገሮች ሁሉ አንድ በአንድ ቢጻፉ ኖሮ የማጻፉትን መጻሕፍት ዓለም ራሱ መሸከም ባልቻለም ነበር።

**ቁ**. 15–17 ኢየሱስ ለጴጥሮስ ሦስት ጊዜ "አንተ ከእነዚህ ሰዎች እኔን ይበልጥ ትወደኛለህ?" ብሎ ጠየቀ። ደግሞም እኛን "እናንተ ከእነዚህ ሰዎች እኔን ይበልጥ ትወዱኛላችሁን?" ብሎ ይጠይቀናል። ኢየሱስ የእኛን መጥፋትን፣ ተስፋ መቁረጥ፣ ዝለትን እንዲገልጽና እንዲሰማም አይፈልግም። ኢየሱስ ከእኛ ብቻ "እኔ አንተን እወዳለሁ" የሚለውን ለመስማት ይፈልጋል።

**ቁ**. 18,19–22 ኢየሱስ ለደቀ መዛሙርቱ ፍቅርን እንዲያደርጉ ፈልጎና ራሱን እንዲከተሉ ተናገራቸው። በዚህ መንገድ የእኛ መሠረታዊ ፍላጐታችንን ትተን የተልዕኮ ቀሕይወታችንና የመስቀሉን መንገድ መሄድ ነው። በዚህ መንገድ የምንሄድ ከሆነ ጌታ የሚናገረው መከበርን ነው። እኛ ደግሞ በየትኛውም በመከራ መንገድ ጌታን ተቀብለን ልንከተል እንችላለን?

**ቁ**. 20–23 ኢየሱስ ደቀ መዛሙርቱን በልዩ ልዩ መንገድ ጠቃሚ አድርጓል። ጴጥሮስና ዮሐንስ አንድ ሥራ ተቀበሉ። ነገር ግን ይህንን ሥራ የሚያደርጉበት መንገድ ልዩ ነው። እኛ ሌሎች ሰዎችን ሳናወዳድር ጌታ ለእኛ የሰጠውን ሥራ እናድርግ።

**ቁ**. 24,25 ዮሐንስ የኢየሱስን ታላቅ ፍቅር በፊደል በመጻፍ በጌታ ውስጥ የዘላለም ሕይወት መኖሩን መስክሯል።

**እንጸልይ፦– ጌታ ሆይ፤ ኢየሱስ የሰጠውን ተልዕኮ በሕይወት እያለን እንድንፈጽም እርዳን፤ አሜን!**

1. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል ዋና ሀሳብ**

2. **ከመፅሐፍ ቅዱስ ክፍል የተሰማውን ስሜት**

3. **እግዚአብሔር ምን አለ? ማን ነው?**

4. **የተቀበልከው ፀጋና ምስጋና**

5. **ትምህርት**

6. **ትግበራ (በስራ ላይ ማዋል)**

7. **ፀሎት**